

የኢትዮጵያ ቋንቋዎች አካዴሚ
የሳይንስና ቴክኖሎጂ ቃላት ስያሜ ፕሮጀክት

ACADEMY OF ETHIOPIAN LANGUAGES
SCIENCE AND TECHNOLOGY TERMS TRANSLATION PROJECT

# የአማርኛ የኤሌክትሮ ሜካኒክ መዝገበ ቃላት

# AMHARIC DICTIONARY OF ELECTRO-MECHANICS

የኢትዮጵያ ቋንቋዎች አካዳሚ

የሳይንስና ቴክኖሎጂ ቃላት ስያሜ ፕሮጀክት

ACADEMY OF ETHIOPIAN LANGUAGES

SCIENCE AND TECHNOLOGY TERMS TRANSLATION PROJECT

# የአማርኛ የኤሌክትሮ—ሜካኒካ መዝገበ ቃላት

# AMHARIC DICTIONARY OF ELECTRO-MECHANICAL TERMS


አዘጋጆች:— ታከለ ታደሰ
ደበበ ሰይፉ*
ጌታቸው ብዙነህ
ሀይሉ አየለ



1978 1986

አዲስ አበባ Addis Ababa


---

* በትርጓሜው ስራ ብቻ የተካፈሉ


From the Library of
ፍሥሐ አጥላው ወልደ ዮሐንስ
FESSEHA ATLAW WOLDE YOHANNES

# ማሳሰቢያ

ይህ መዝገበ ቃላት በተቻለ መጠን ከፍተኛ ጥረት ተደርጎበት የተዘጋጀ ሲሆን፣ በኢትዮጵያ ቋንቋዎች አካዴሚ ጉባኤ ወደፊት ገና የሚፀድቅ መሆኑን እያሳሰብን በመገንዘብ ቃላቱ ላይ ገንቢ አስተያየት ለመስጠት የሚፈልግ ሁሉ ቀጥሎ ባለው አድራሻ አስተያየቱን በፅሁፍ ሊሰጥ የሚችል መሆኑን እንገልፃለን::


የኢትዮጵያ ቋንቋዎች አካዴሚ

ፖ.ሳ.ቁ. 1907

ባህል ሚኒስቴር

አዲስ አበባ


የመዝገበ ቃላቱ የባለቤትነት መብት በህግ የተጠበቀ ነው::

ይዘት = CONTENTS

## ም ስ ጋ ና

ለዚህ ለሳይንስና ቴክኖሎጂ ቃላት ስያሜ ፕሮጀክት አስፈላጊውን የገንዘብ እርዳታ ላደረገው ለተባበሩት መንግስታት የሳይንስና ቴክኖሎጂ ለልማት ፋይናንሻል ሲስተም /UNFSSTD / የኢትዮጵያ አካዴሚ ከፍተኛ ምስጋና ያቀርባል::

## ACKNOWLEDGEMENT

The Academy of Ethiopian Languages expresses its profound gratitude to the United Nations Financial system for Science and Technology for Development (UNFSSTD) for sponsoring this Project (STTTP).

# <u>መቅድም</u>

ይህ ኤሌክትሮ ሜካኒክ የአማርኛ መዝገበ ቃላት የኢትዮጵያ ቋንቋዎች አካዳሚ የሳይንስና ቴክኖሎጂ ቃላት ስያሜ ፕሮጀክት ካዘጋጃቸው 13 መዝገበ ቃላት መካከል አንዱ ነው። በአጠቃላይ በፕሮጀክቱ የተዘጋጁት የሳይንስና ቴክኖሎጂ ስያሜ መዝገበ ቃላት ከዚህ በታች ለተመለከቱት የሙያ ዘርፎች ሲሆን፣ ምንጭ ቋንቋውም/Source Language/ እንግሊዝኛ ነው።

1. ግብርና - AGRICULTURE
2. ቦታኒ - BOTANY (BIOLOGY I)
3. ህንፃ ኮንስትራክሽን - BUILDING CONSTRUCTION (TECHNOLOGY I)
4. ኬሚስትሪ - CHEMISTRY
5. ኤሌክትሮ ሜካኒክስ - ELECTRO-MECHANICS
6. ጂኦግራፊ - GEOGRAPHY
7. ጂኦሎጂ - GEOLOGY
8. ማቴማቲክስ /ማቴማቲካ/ - MATHEMATICS
9. ህክምና - MEDICINE
10. ኑትሪሽን - NUTRITION
11. ፊዚክስ /ፊዚካ/ - PHYSICS
12. ስታቲስቲክስ /ስታቲስቲካ/ - STATISTICS
13. ዞኦሎጂ - ZOOLOGY

እነዚህ በፕሮጀክት ደረጃ የተሰሩት የሳይንስና ቴክኖሎጂ ስያሜ መዝገበ ቃላት የመደበኛ የመዝገበ ቃላት አሰራርን ዘዴ ሙሉ በሙሉ በመከተል ሳይሆን በየሙያው ዘርፍ የተሰየሙትን አዳዲስ ቃላት ለማስተዋወቅና ለማበራራት አመቺ በሆነ የአሰራር ስልት እያንዓንዱን ስያሜ በፊደል ተራ በማስገባት ነው። ስለሆነም የተሰየሙት ቃላት አመቺ በሆነ መድረክ ተሰራጭተውና ተፈትነው ተቀባይነት ያገኙትና በአካዳሚው የፀደቁት ወደፊት በመደበኛ የመዝገበ ቃላት አሰራር በአንድነት ተጠቃለው <u>የሳይንስና ቴክኖሎጂ ስያሜ መዝገበ ቃላት</u> በሚል ርእስ ታትመው ይወጣሉ። ይህ መዝገበ ቃላትና ሌሎቹም ቀጥለው የተመለከቱትን 3 ዋና ዋና ክፍሎች ይዘው ይገኛሉ።

1. የቃላት ማብራሪያ ክፍል
2. የአማርኛ-እንግሊዝኛ የቃላት ዝርዝር
3. የእንግሊዝኛ-አማርኛ የቃላት ዝርዝር

የቃላት ማብራሪያው ክፍል በየሙያው ዘርፍ ስያሜ ከተሰጣቸው አጠቃላይ ቃላት ውስጥ ሣምሳ በመቶውን ያህል መርጦ የቃላቱን ፅንሰ ሃሳብ በአረፍተ ነገርና አስፈላጊም በሆነበት ቦታ በስእል አማካኝነት የሚገልፅ ክፍል ነው።

በየሙያው ዘርፍ ከተሰየሙት ቃላት ውስጥ ሃምሳ በመቶው ብቻ ተወስኖ የተብራራበት ዋናው ምክንያት ቀደም ሲል እንደተገለፀው የተሰየሙት ቃላት በስራው ተሰራጭተውና ተፈትነው ተቀባይነት ከማግኘታቸውና በመፀደቃቸው በፊት ሁሉንም ማብራራት አስፈላጊ ባለመሆኑ ነው። ስለሆነም ከላይ ከተጠቀሰው የሳይንስና ቴክኖሎጂ ስያሜ መዝገበ ቃላት ታትሞ በሚወጣበት ጊዜ ዋናና ወሳኝ የሆኑት ስያሜዎች ሁሉ ይብራራሉ። በየሙያው ዘርፍ መዝገበ ቃላት ውስጥ ምን ያህል እንደተሰየሙ በማሳየትና ልዩ ልዩ ሳይንስና ቴክኖሎጂ ነክ ፅሁፎች በአማርኛም ሆነ በእንግሊዝኛ በሚነበቡበት ጊዜ አቻ ስያሜዎችን ለማወቅ እንዲረዳ በየመዝገበ ቃላቱ ውስጥ የአማርኛ-እንግሊዝኛ፣ የእንግሊዝኛ-አማርኛ የቃላት ዝርዝር ይገኛል።

አንዳንድ የእንግሊዝኛ ስያሜዎች የአማርኛ አቻ ስያሜ በየሙያው ዘርፍ በሚሰጣቸው ወቅት በልዩ ልዩ ቃላት ተሰይመው ይገኛሉ። በአንፃሩም ለተለያዩ የእንግሊዝኛ ስያሜዎች አንድ የአማርኛ ስያሜ የሚያገለግልበት ሁኔታ በየመዝገበ ቃላቱ ዝግጅት ውስጥ ተከስቷል።

ከዚህም በቀር ለአንድ የእንግሊዝኛ ስያሜ ሁለትና ሶስት አማራጭ ስያሜዎች አልፎ አልፎ በየመዝገበ ቃላቱ ውስጥ ተሰጥቶ ሲገኝ ለዘለቄታው ተቀባይነት የሚያገኘው ስያሜ ወደፊት ጊዜ ይፈታዋል።

በፕሮጀክቱ የስራ ሂደት ወቅት በየሙያው ዘርፍ የአማርኛ ስያሜ የተሰጣቸው ቃላት ዝርዝር እየተባዛ ለአስተያየት በየስፍራው በመሰራጨቱ ከግለሰቦችና ድርጅቶች በተገኙ ገንቢ አስተያየቶች አንዳንድ የስያሜ ለውጥ ከመደረጉም በላይ፣ ፕሮጀክቱ በየጊዜው ባካሄዳቸው ዎርክሾፖችና ሴሚናሮች የስያሜ ማሻሻልና ለውጥ ተደርጓል። ሆኖም በየጊዜው የተደረጉትን አንዳንድ የስያሜ ለውጦች በትክክል በሚገኙበት ቦታ ሁሉ ለማረም አዳጋች በመሆኑ፣ በዚህና በሌሎችም መዝገበ ቃላት ውስጥ ሊገኝ የሚችል አንዳንድ የስያሜ መዘበራረቅ ወደፊት የሳይንስና ቴክኖሎጂ ስያሜ መዝገበ ቃላት በሚዘጋጅበት ጊዜ ጥራት ያገኛል።

በኢትዮጵያ ቋንቋዎች አካዳሚ የሳይንስና ቴክኖሎጂ ቃላት ስያሜ ፕሮጀክት የተሰየሙት ቃላት በአጠቃላይ ከ15,000 በላይ ሲሆኑ፣ አብዛኛዎቹ ስያሜዎች የሁለተኛ ደረጃንና የአንደኛን አመት የዩኒቨርሲቲ ትምህርት በአማርኛ ቋንቋ ለመስጠት የሚያስችሉ መሆናቸው ይታመናል።

በየሙያው ዘርፍ ጥቂት የናሙና ምንባቦች ፕሬጀክቱ አዘጋጅቶ ለሙከራ አውጥቷል።

| | |
|---|---|
| የፕሮጀክቱ ዳይሬክተር | የፕሮጀክቱ የቴክኒክ አስተባባሪዎች |
| አሰፋ ገብረማርያም ተሰማ<br>የኢትዮጵያ ቋንቋዎች አካዳሚ<br>ዋና ፀሐፊ | ኤርሚያስ ዳኘ /ዶ.ር/<br>ደምሱ ገመዳ /ዶ.ር/ |

# መግቢያ

በኢትዮጵያ ቋንቋዎች አካዳሚ አማካይነት የሳይንስና ቴክኖሎጂን ቃላት በአማርኛ ለመሰየም በወጣው አቅድ መሰረት የኤሌክትሮ መካኒካል ፓኔል 1182 ቃላት ስያሜ አገኘተላቸዋል ቸቸ ዘነዚህም ቃላት ውስጥ 450 ቃላት ማብራሪያ በመስጠት ለዚህ መዝገበ ቃላት አስተዋፅኦ አድርጓል፡፡

በእንግሊዝኛ ቃላት የተገለፁትን ፅንሰ ሃሳቦች የአማርኛ ቃላት ለማግኘት የተጠቀምንባቸው ዘዴያት የሚከተሉት ናቸው፡፡

1. የእንግሊዝኛውን ቃል ምንጭ በመፈለግ በዚያው አይነት የቃል በቃል ለውጥ በአማርኛ ለማግኘት ተሞክሯል፡፡

   ለምሳሌ: Piston - ዘነዘና
   
   Lens - ምስሪት

2. የእንግሊዝኛው ቃል አንድ ሆና ተመሳሳይ የሆነ አንድ የአማርኛ ቃል ለማግኘት ሲያስቸግር አመቺ ሆና ከተገኘ ሃሳቡን በሃረግ በመግለፅና እንደገና ሃረጉን በመጉረድ አንድ ቃል እንዲወጣ በማድረግ ተጠቅመናል፡፡

   ለምሳሌ: Strain - ጭምጽሬ/የጭመት ወርዝም ንጽሬ/
   
   Lock-nut - ቆላሰሪ / ቆላፊ አሳሪ/
   
   V - thread - ሶማጥርስ /ሶስት ማእዘን ጥርስ/

3. በእንግሊዝኛ ቃል የተገለፀው ሃሳብ በአገራችን ከሚገኘው ባህልና ቴክኖሎጂ ጋር በተያያዘ መንገድ ተቀራራቢነት ያላቸውን ቃላት በመውሰድ ትርጓሜያቸው ከፍ እንዲል በማድረግ ሃሳቡን እንዲወክሉ አድርገናል፡፡

   ለምሳሌ: Pin - ቀትርት / የግብርና እቃ/
   
   Rocker arm - መቋናጠ / የሽመና እቃ/
   
   Crucible - ጊርጊራ /አርሚኛ/
   
   Hoe - ከለታ /ጉራጊኛ/
   
   Nipple - ኩዳ /ሻንቅልና/

4. የእንግሊዝኛ ቃል አንድ ሆና ሁለት ወይንም ከዚያ በላይ የሆኑ የአማርኛ ቃላትን በማጣመር ሀሳቡን ለመግለፅ በሚቻልበት ጊዜ በዚህም በመጠቀም ቃላት ለማግኘት ችለናል፡፡

   ለምሳሌ: Mallet - እንጨት መዶሻ
   
   Rasp - እንጨት ሞረድ
   
   Sketch - ተራንድፍ

5. ለአንድ የእንግሊዝኛ ቃል የአማርኛ አቻውን ለማግኘት በማይቻልበት ጊዜ የእንግሊዝኛውን ቃል በመውሰድ ቃሉ በአማርኛ ሰዋሰው ተገዢ እንዲሆን በማድረግ ወደ አማርኛነት ለውጠነዋል፡፡ የዚህ አይነቱ ዘዴ ቃሉ በእንግሊዝኛ በሚረባበት ጊዜ ለያንዳንዱ የእርባታ ቃል የአማርኛ አቻውን ለማስገኘት በማስቻሉ ፍቱን ዘዴ እንደሆነ ተገንዝበናል፡፡

   ለምሳሌ: To anneal - ማነል
   
   Annealed - እንል

Annealing - አነሳ
To temper - መተምፐር
Tempered - ትምፕር
Tempering - ትምፐራ

6. አንዳንዱ የእንግሊዝኛ ቃላት ከላይ በተገለፁት ዘዴዎች ሆነ በሌላ ዘዴ ምንም አይነት ቃል ለማግኘት በማይቻልበት ጊዜ የእንግሊዝኛውን ቃል ለአማርኛ አነጋገር እንዲያመች እየተደረገ ተወርሷል::

ለምሳሌ: Carburetor - ካቡሬተር
Entropy - አንትረቢ
Enthalpy - አንታልቢ

7. አንዳንዱ የእንግሊዝኛ ቃላት በመጀመሪያ ፅንሰ ሃሳበትን በአመነጩት ሊቃውንት ስሞች ቀዳሚነት የተሰየሙ ሆነው ሲገኙ የሊቃውንቱ ስሞች ሳይለወጡ ተወስደዋል::

ለምሳሌ: Otto cycle - አቶ ኡደት
Diesel cycle - ዲዝል ኡደት
Carnot cycle - ካርኖ ኡደት

8. በአማርኛ ሰዋሰው መዋቅር መሰረት በቃላት እርባታ ሊገኙ የሚችሉት የቃላት ቅርፆች ሁሉ እስከአሁን በብዛት ሲሰራባቸው ባይታይም በሰዋሰዋዊ ህጉ መሰረት በእርባታ ሊገኙ የሚችሉትን ቃላት በመፈለግ በዚሁ ዘዴ ርባታው የተገኙት ቃላት በእንግሊዝኛ ካሉት ቃላት ጋር የሃሳብ ዝምድና ያላቸው ሆነው ከተገኙ እንደነዚህ ያሉት ቃላት የተፈለጉትን ሃሳቦች እንዲወክሉ ተደርገዋል::

ለምሳሌ: Clearance - ግልጠት
Flow - ርሰት
Combustion - ነደት

9. አንዳንዱ ጊዜ አማርኛ እድገቱ ባስገኘው ፍሬ በመጠቀም በእንግሊዝኛ የተገለፁት ሃሳቦች ተቃራኒ ፅንሰ ሃሳቦች ይዘው ሲገኙ የአማርኛ አቻቸው ኢ በተባለው ባእድ መነሻ በመጠቀም የተፈለገውን የአማርኛ ቃል ለማግኘት ችለናል::

ለምሳሌ: Clearance - ግልጠት
Interference - ኢግልጠት

10. አንድ ወይንም ሁለት የእንግሊዝኛ ቃላት የሚገልፁትን ሃሳብ በአማርኛ ጥምር ቃላት ለመግለፅ በምንገደድበት ጊዜ የአማርኛ ጥምር ቃላት መዋቅር የግእዝን ህግ ተከትለው ቢዋቀሩ የተሻለ ተነባቢነትና አጭርነት ሊኖራቸው በሚችልበት ጊዜ በግእዙ ህግ በማጣመር ዘዴ ተጠቅመናል::

ለምሳሌ: Wind mill - ሽክርክረ ነፋስ
Vapour power - እቅመ ተን

ሀምበድ Pentode

ባለአምስት መመጧ አየር አልባ ቀለሀ

ሀ—ቡሎን U-bolt

የሀን ፊደል መስሉ የተሰራ በሁለቱም አገሮቹ ላይ ጥርሶች የወጡለት የቡሎን አይነት /ስእል 1 ይመልከቱ/

ሀይለ አውድ Field strength (intensity)

የማንኛውም /የኤሌክትሪክ ወይም የማግኔት ወይም ሌላ/ አውድ ጥንካሬ መጠን:: የኤሌክትሪክ ሃይለ አውድ የሚመጠነው ወይም የሚለካው አውዱ አወንታ በሆነ አንድ ኩሎምብ የኤሌክትሪክ ሙሌት ላይ በሚፈጥረው ሃይል / Force / ነው

ሁለት አቅጣጫ ሞተር Double acting engine

አንድ ዘነዘኔ በበርሚሉ ውስጥ ሆና በሁለቱም ጫፎች በኩል በየተራ በሚፈጠር ግፊት ምክንያት እየተዘናዘነ የሚሰራበት የሞተር አይነት

ሀዋስ Cell

በኤሌክትሪክ ባትሪ ውስጥ ሁለት ጫፎች ያሉትና መሰረታዊ ከኬሚካዊ ሃይል የኤሌክትሪክ ሃይል ለማመንጨት የሚችል

## ለ

ለቃቂ Emitter

የኤሌክትሪክ ሙሌት ተሸካሚያት የሚመነጩበት የትራንዚስተር አንድ ክፍል

ሉንቃ ክፍክድ Globe (stop) valve

ጠፍጣፋ ክብ መቆጣጠሪያ በኳስ መሰል ቀፎ ውስጥ ሆና ፍሰትን ለመቆጣጠር የሚያገለግል ከዋን /ስእል 2 ይመልከቱ/

ላእለቀበላ Supercharging

ውስጠ ቃጠሎ ሞተር በራሱ ጥረት ከከባቢአየር ወደበርሚሎቹ ውስጥ ከሚያስገባበት ግፊት በላይ በሆነ መጠን የማስገባት ዘዴ

ላይ መቆሚያ Top dead centre

በዘንዘኔ በሚሰራ ሞተር ውስጥ የአመቃ ወይም የማስወጣት ሂደት ልክ ሲያበቃ ዘነዘነውና መዘወሪያ ኩላብ ያሉበት ሁኔታ

ላይ እይታ Top view

አንድ ነገር በአናቱ በኩል ሲታይ እንደሚመስለው ተደርጎ የተሰራ አንጥ ወይም ተራ ንድፍ

ሌምበ ማሸጊያ Lip seal

በተለይ አንዱ በሚንቀሳቀስና ሌላው በማይንቀሳቀስ ሁለት አካላት መካከል ፈሳሽ ወይም ቀባት እንዳይተላለፍ የሚያደርግ የማገጃ አይነት

ልምጣዊ ጫና Flextural stress

በ[illegible]ነት ምክንያት አንድ ነገር ሲጎብጥ የሚፈጠረው ውስጣዊ አመቃና ውጥረት

ልምጥምጥ Flexible

በቀላል ሃይል ሳይሰነጠቅና ሳይሰበር ተለምጦ የሚዘረጋ ነገር

ልቀት/የኤሌክትሮን/ Emission (electron)

በአንድ ነገር ውስጥ ያሉ ኤሌክትሮኖች በሙቀት ወይም በብርሃን ሃይል አማካይነት በሚያገኙት ከፍተኛ ሃይል የአሉበትን አካል ለቀው ሊወጡ

ልከማአዘን Angle

ሁለት ቀጥታ መስመሮች አንድ ነጥብ ላይ ሲገናኙ ወይንም ሁለት ጠለሳዎች በአንድ መስመር ላይ ሲገናኙ አንዱ መስመር ከሌላው መስመር ወይንም አንዱ ጠለሳ ከሌላው ጠለሳ ጋር ሲተያይ የሚፈጥረው መቀንነት

ልከርገብገብታ Amplitude

በየጊዜው የሚለዋወጥ ከረንቲ ወይም ማንኛቸውም ነገር የሚደርስበት ከፍተኛ መጠን /ከታች ያለውን ስእል ይመልከቱ/

ልከርገብገብታ ርክርክ/ልር/ Amplitude Modulation (AM)

የሞገድን ልከርገብገብታ መለዋወጥ:: በመካከለኛ ሞገድ የሚተላለፈው የሬድዮ ስርጭት ልከርገብገብቱው የተረከረከ የራድዮ ሞገድ ነው:: ልከርገብገብታውም የሚለዋወጠው በሚተላለፈው የድምፅ ሞገድ መጠን ትልቀነትና ትንሽነት ይሆናል /ስእል 3 ይመልከቱ/

ልክ Gauge

የሽቦ፣ የቆርቆሮ፣ ወይንም የብረት ዘንግ የመሳሰሉትን የውፍረት መጠን ማመልከቻ

ልካሽ መስመር Dimension line

በአንጥ ንድፍ ስራ የማናቸውንም ነገር መጠን የሚያመለክት መስመር

ልይታዊ Differential

በሁለት የመኪና ጎማዎች መካከል ሆኖ ፍጥነታቸውን የሚያጣጥም የጥርሶች ገጥምጥም

ልጠት ጫና Elastic limit

አንድ ጥጥር ነገር ከመለጠጥ ደረጃ አልፎ ብልሽት ደረጃ ሳይደርስ ሊቋቋመው የሚ ትለው ከፍተኛ ጫና

መ

መሃል ነጣይ ሃይል Centrifugal force

አንድ ነገር በአንድ ማእከል ዙሪያ ሲዞር የሚከሰተውን ማሃለሳቢ ሃይል በመቃረን በአከበዘንጋዊ አቅጣጫ ወደ ውጪ የሚገተት አስፈንጣሪ ሃይል

መሀለሳቢ ሃይል Centripetal force

አንድ ነገር በአንድ ማእከል ዙሪያ ሲዞር ሊዞርበት ከተወሰነለት መስመር እንዳ ይወጣ የሚከላከል ሳቢ ሃይል

መለኪያ Gauge

ልክንና ቅርፅን የመስፈሪያ መሳሪያ

መሳሽ Commutator

የቀጥተኛ ከረንቲ ሞተር ወይም አመንጪ አንድ ክፍል ሆኖ ከብሩሹ ጋር በመሆን ከተሽከርካሪው የሞተሩ ክፍል ጋር የኤሌክትሪክ ግንኙነት ለማድረግ የሚረዳና ተለዋዋጭ የሆነውንም ከረንቲ ለማቃናት የሚያገዝ

መሳሽዘዊ Caster angle

የፊት ጎማን ከተሽከርካሪው ጋር የሚያገናኘው ዋናው ቀተርተ ወደፊት ወይንም ወደ ኋላ እንዲያዘነብል ሲደረግ እንዲኖረው የሚያስፈልገው የዘዊ መጠን



1. ሀ—ቡሎን



2. ሳንቃ ክፍከድ







3. ለከርግብግብታ ርክርክ



5. መር



4. መርፍ ክፍከድ



6. መስ ቀለኛ ሙላ

8.



መዘዋወሪያ ኩላብ



9. መቋረጊያ



10. ሰናግ ቀተርት



12. ቀለፍ



11. ስንብጥ አሰሪ



13. ቀለንገት

መረከረከ Modulate

የአንድ ኤሌክትሪክ ሞገድ ለከአርገብገብ ታ፣ ድግግሞሽ ወይም ገፅታ በተወሰነ ሁኔታ መለዋወጥ፤ በኤሌክትሮን ዉራ ውስጥ ያሉት ኤሌክትሮች ፍጥነት መለዋወጥ

መሪ Steering wheel

የተሽከርካሪ ወይም የመርከብ ነጂ በእጆቹ ወደግራና ቀኝ እያዟዟረ የተሽከርካሪውን ወይም የመርከቡን አቅጣጫ የሚቆጣጠርበት ሽክርክር

መሪ ዘንግ Steering column

በተሽከርካሪ መሪና በመሪ ሳጥን መካከል ያለው ዘንግ

መርፌ ክፍክድ Needle valve

በጣም ቀጭን የሆነ ዘንግ በአቻው ክብ ቀዳዳ ውስጥ ተሰክቶ ፍሰትን የሚቆጣጠር እቃ /ስእል 4 ይመልከቱ/

መሮ Chisel

በመዶሻ እየተመታ ጫፉ ለመቀረጫ ወይንም ለመጥረቢያ የሚያገለግል አጭር ጠፍጣፍ ያለ የእጅ ማቀለጠፊያ /ስእል 5 ይመልከቱ/

መሰርሰሪያ Drill bit

ጥጥር የሆነን ቀኅ ለመብሳት የሚያገለግል ተሽከርካሪ መብሻ

መስቀለኛ ሙሳ Universal joint

ሁለት በዘዊ የተለያዩ ኩላቦች በአንድ ጠለላ ውስጥ ተገናኝተው ከአንዱ ኩላብ ወደሌላው አቀም ለማስተላለፍ ኩላቦቹ ያለችግር እንዲሽከረከሩ የሚያደርግ መገናኛ አካል /ስእል 6 ይመልከቱ/

መቀርጠፊያ Shear

ብረቶችን የሚቀረጥፍ መሳሪያ

መቐርጠፍ ብርታት Shearing strength

አንድ ነገር ከመቐርጠፉ በፊት ሊቋቋመው የሚችለው ከፍተኛው የቀርጠፋ ጫና

መቀነት መጋዝ Band saw

በሁለት በከራያች ተወጥሮ በሞተር ሃይል እየተሽከረከረ እንጨት ለመቁረጥ የሚያገለግል መጋዝ

መቀጥቀጥ Forge(v)

ሙቅ የሆነ ብረታብረትን በጫና ሃይል የሚፈለገውን ቅርፅ እንዲያገኝ ማድረግ

መቈናጥ Rocker arm

በውስጠ ቃጠሎሽ ሞተር ውስጥ በገፊ ዘንግ እየተንቀሳቀሰ የሞተርን ክፍክድ የሚያንቀሳቅስ መፈንቀል መሰል አካል

መቋሚያ Dead centre

በዝንዟኔ የሚንቀሳቀስ ነገር አለፍ ለመሄድ የማይችልበት የመጨረሻ የእንቅስቃሴ ወሰን

መቆንጠጫ Clip

ሁለት ወይም ከሁለት የሚበልጡ ነገሮችን ቆንጥጦ ለመያዝ የሚያገለግል ነገር

መቆ፟ጣጠሪያ ከፍከድ Check valve

ፈሳሸር በአንድ አቅጣጫ ብቻ እንዲፈስ የሚያደርግና ፈሳሸሩ ወደመጣበት በታ እንዳይመ፟ለስ የሚቆጣጠር ከፍከድ

መነሻ መስመር Datum line (Reference line)

ዘፄ ወይንም ቀጥታ መስመር ለመለካት በሚፈለገበት ጊዜ የመለኪያው መነሻ

መንታ ኡደት Dual cycle

የሙቀት ማስገቢያያች ሂደቶች ኢተለዋዋጭ ይዘት እና ኢተለዋዋጭ ግፊት ሆነው የቀሩት ሂደቶች እንደ ኦቶ እና እንደ ዲዘል የሆኑ ሂደቶች ያሉት የኡደት አይነት

መንደደገለት መጠን Heat valve

አንድ የተወሰነ ይዘት ያለው ቁስ የተወሰነ ግፊት ተጠብቆለት ሙሉ በሙሉ ከነደደ በኋላ የመነጨው የሙቀት መጠን

መዋቀረፍቻ . Test rig

በምርምር ስራ ውስጥ ለሙከራ የሚያገለግል መኪናና ሌሎች አካላት በአንድነት ተጣምደው የሚገኙበት ቀንጅት

መዋ፟ደድ Mesh

አንዱ ጥርስ ሌላውን እንዲነዳው ወይንም እንዲያንቀሳቅሰው ከሌላው ጋር ሲጣመድ

መዋደድ ሃይል Force fit

ሃይል በመጠቀም የአካላት በኢገልጠት ማዋ፟ደድ

መዘወሪያ Crank

አንዱን ነገር እንዲሽከረከር ለማድረግ የሚረዳ ወሰጋጣ ማቀሳጠፊያ

መዘዋወሪያ ቀተርት Crank pin

የመዘወሪያ ኩላብ አካል ሆኖ ከአገናኝ ዘንግ ጋር የሚቀናጅ አጭር ወፍራም ቀተርት

መዘዋወሪያ ኩላብ Crank shaft

ቀጥታና መዘወሪያ አካላት በአንድነት የሚገኙበት የኩላብ አይነት /ስእል 8 ይመልከቱ/

መዝምገግ Drawing (for wires)

ብረታብረትን ከወፍራም ወደ ቀጭን መጠን በተለየ እቃ ውስጥ እየመዘዙ የማውጣት ሂደት

መደላደል ቱብ Bushing

ከለስላሳ ብረታብረት የሚሰራ በቋሚና በተሽከርካሪ አካላት መካከል የሚገጠም በጣም አጭር የሆነ ቱብ

መደብ Ground

አንድን የኤሌክዙር ወይም የኤሌክትሪክ አቃና ከመሬት ጋር የሚያገናኝ /አውቆም ሆነ ባለማወቅ ሊፈጠር ይችላል/ አስተላላፊ ብረትማ መስመር:: አብዛኛውን ጊዜ በኤሌክዙር ውስጥ የሚገኝን ነጥብ ችሎታ /ወይም ሽልቴጅ/ የሚለካው ከመደቡ ጋር በማነፃፀር ሲሆን የመደቡ ችሎታ ዜሮ ሽልት ተብሎ ይወሰዳል

መደሸና Lagging

ከልዩ ልዩ አቃዎችና ቧምቧዎች ውስጥ ሙቀት እንዳያመልጥ ለመሸፈን የሚያገለግል እንደአስቤስቶስ ያለ ቁስ

መዷን ክፍክድ Poppet valve

በወለፈንጂ ወይም በመቹፕ አማካይነት እየተዘናዘነ የሚሰራ የእንጉዳይ መልክ ያለው ክፍክድ:: ስእል 69 ይመልከቱ

መገጣጠም Assemble

የመካኒዝምን የመኪናን ወይንም የከዋኝን አካላት አብረው በሚሰሩበት ሁኔታ እንዲገኙ ማድረግ

መጋቢ/መስመሮች/ Feeder (lines)

ከአንድ የኤሌክትሪክ ምንጭ ወይም ሌላ መሳሪያ ወደ ሌላ የኤሌክትሪክ መሳሪያ ገቢውን ሃይል የሚያስተላልፉ መስመሮች:: የሬድዮ ሞገዶች ከአመንጭ መሳሪያው ወጥተዉ ወደ አሰራጭው አንቴና የሚወስዱት በመጋቢ መስመሮች ነው

መጠምጠሚያ Core (magnetic)

የጥንጥንን ማግኔታዊ ጠባይ ከፍ ለማድረግ የሚረዳ ብረት ሆኖ በላይ ላይ ከረንት ተሸካሚ የሆኑ አስተላላፊዎች የሚጠመጠሙበት

መጠቆሚያ Center punch

በብረታ ብረቶች ላይ የተደረጉትን ነጥብ ምልክቶች ወይንም ቀዳዳዎችን በመጠኑ ለማስፋት የሚያገለግል አጭር ሹል ማቀላጠፊያ

መጠባበቂያ አሃዝ Safety factor

አንድን ነገር ልክ ሊሰብረው ወይም ሊያበላሸው የሚችለው ሸክም የተፈቀደለትን ተሸክሞ መደበኛ ስራውን ለማከናወን ከሚችለው ሸክም ጋር ሲወዳደር የሚገኘው ንፃሬ

መጠነድገት Gain

አንድ አግናኝ የተቀበለው የኤሌክትሪክ ሲግናል ልከርገብገብታ ወይም ጉልበት የሚያድግበት መጠን

መጥኜመፍቻ Torque wrench

ቡሎኖችን በተወሰነላቸው ጥምዘዛ መጠን እንዲታሰሩ ለክቶ የሚያስር ልዩ የእጅ ማቀላጠፊያ

መጣኝ ከፍከፎ Throttle valve

በፓምፕ ወይም በአማቂና በሌላ መኪና መካከል ተገጥሞ የፈሳሸርን ፍሰት የሚቆጣጠር ወይም የሚያስተካክል ከፋኝ

መጧጭ ፓምፕ Ejector

ፈሳሸር በፍጥነት በውስጡ ሲያልፍ የገፊት ዘበጥ በመፍጠር ሌላ ፈሳሸርን መጠ የሚተፋ አቃ

መጥረጊያ Reamer

በብረታብረት ላይ የተሰራውን ቀዳዳ ለማለስለስ፣ ለማስተካከል ወይም ሰፋ ለማድረግ የሚያገለግል ልዩ ማቀላጠፊያ /ስእል 9 ይመልከቱ/

መፀሄት ባህሪይ Characteristics curve

በሁለት ወይም ከዚህ በላይ በሆኑ የአንድ የኤሌክትሪክ ከፋኝ መገለጫ ባህሪያት መሀከል ያለውን ግንኙነት የሚገልፅ ስእላዊ መገለጫ

መፈንቀያ Crowbar

እንደመፈንቀል የሚያገለግል ጫፉ ጠፍጣፍ ያለ ጎባጣ አረብረት

መፈንቀል Lever

በአንድ በታ ላይ ተመርኩዞ አንድ ነገርን ለማንሳት ለማንፏቀቅ ወይንም ለመፈንቀል የሚረዳ መፈንቀያ

መፍቻ Wrench (Spanner)

የቡሎኖችን ራስ በመያዝ ቡሎኖችን ለማጥበቅ ወይም ለመፍታት የሚያገለግል በልዩ ልዩ መልክ የተሰራ ማቀላጠፊያ

ሙሳ Joint

ሁለት ወይንም ከሁለት በላይ የሆኑ መካኒካዊ ክፍሎች የተገኙበት አካል

ሙሌት/ የኤሌክትሪክ/ Charge (electric)

የቁስ አካል ቀዳሚ ክፍልፋዮች መሰረታዊ ባህሪይ ሲሆን ሙሌቱ አወንታ ወይም አሉታ ወይም ነፁ ሊሆን ይችላል

ሙሌት ተሸካሚ Charge carrier

በከፊል አስተላላፊ ውስጥ ተንቀሳቃሽና ኤሌክትሪክ አስተላላፊ ኤሌክትሮኖችና አይ ነበጉያች

ሙቀት ሰፍናጊ Heatsink

እንደ ትራንዚስተር ያሉ የኤሌክትሮኒክ ስቶፍ ምንዝሮች በሚሰሩበት ጊዜ በውስጣቸው የሚፈጠረው ሙቀት ከፍ ብሎ እንዳያበላሻቸው የሚፈጠረውን ሙቀት ለመውሰድ ወይም ለመምጠጥ የሚችል ብረትማ ሸፋን

ሙቀት አለዋዋጭ Heat exchanger

ሁለት ፈሳሸሮች ተቀላቅለው ወይንም ሳይቀላቀሉ ሙቀታቸውን ከአንዱ ወደ ሌላው ሊያስተላልፉ የሚተሉበት አቃ

ማለፊያ Base

በለቃቂና በተቀጣይ የትራንዚስተር ክፍሎች መሃል የሚገኝና ከለቃቂው የሚወጡት የኤሌክትሪክ ሙሌት ተሸካሚያች ወደ ተቀባዩ ከመድረሳቸው በፊት የሚያልፉበት ክፍል ነው

ማመቻቻ ኩላብ Mandrel

በርሜላዊ ሆና ረዝም ያለን ውስጠ ክፍት አካል ከውጭ በክል ሙሉ በሙሉ በአዋዲ መኪና መስራት ሲያስፈልግ በውስጥ በኩል ለመያዝ የሚያገለግል ከኩላብና ከሌሎች አካላት የተሰራ ማቀላጠፊያ

ማስማማት Synchronize

የፍጥነት አንቀሳቃሽ ጥርስ ሲለወጥ ሊጠመዱ የሚፈለጉትን ጥርሶች በተመሳሳይ ፍጥነት እንዲሽከረከሩ ማድረግ

ማስረግ Impregnate

ፈሳሽን ውንፊት ባለው ጠጣር ነገር ውስጥ አስገብቶ በማርጋት የጠጣሩ አንዳንድ ባህሪያ ለመለወጥ መቻል

ማስተንፈሻ ክፍክድ Safety valve

ፈሳሽርን በያዘ መካኒካዊ ስርአት ውስጥ የፈሳሽርን ግፊት ከተፈለገው መጠን እንዳይበልጥ የሚቆጣጠር ክዳን

ማስወገድ Scavenge

በሁለት ምት የሚሰራ ተዘናዛኝ ሞተር ውስጥ ጭስ መውጣት እንደጀመረ ንፁህ የአየርና የነዳጅ ድብልቅ ወደበርሜሉ እየገባ ጭሱን ሲያስወግደው

ማሸት Lapping

በልዩ ለስላሳ ነገሮችና ቀባቶች ብረታብረቶችን አየፊቶች ማስተካከል

ማሸጊያ Seal

ፈሳሽር እንዳይባክን ወይንም ወደአልተፈለገበት ቦታ እንዳይሄድ የሚከለክል አካል

ማቀናጃ Coupling (network)

ከአንዱ ወደ ሌላው የሚተላለፈው የኤሌክትሪክ ሃይል ከፍተኛ እንዲሆን ወይም የተፈለገውን ባህሪ እንዲኖረው ለማድረግ የሚተል በሁለት ኤሌክዞሮች መካከል የሚውል አቃ

ማቀጣጠያ ጥንጥን Ignition coil

በማግኒታዊ እርዳ መለክ ያጠራቀመውን ሃይል በቀፀበት በከፍተኛ ሽልቱድ በመለ
ቀቀ በብልጭታ ዘንግ አማካይነት የአየርና የነዳጅ ቅልቅልን ለማቀጣጠል የሚተል ጥንጥን

ማቀፍ Crankcase

በውስጠ ቃጠሎ ሞተር ውስጥ የኩላቡን አካባቢ አቅፍ የሚይዝ የሞተር አካል

ማበከን Dissipate

ከረንቲ በክል ውስጥ ሲያልፍ ወደ ሙቀት የመለወጥ የመጥፋትን ሁኔታ የሚያ
መለክት /ብክነት - Dissipation/

ማትነኛ Evaporator

በሙቀት አማካይነት ፈሳሽ ወደ ተን የሚለወጥበት ማናቸውም አይነት ከዋኝ

ማኘስ Anneal

ከብረታብረትና ከመስተዋት የተሰሩ ነገሮችን በማሞቅና በማቀዝቀዝ ተፈርካሽነታቸው እንዲቀንስ ማድረግ

ማንሻ Hoist

በከራዎች ከሰንሰለት፣ ከገመድ ወይንም ከካቦ ጋር ተገጣጥመው ማንሳት ከተፈለገው ከብደት በላይ ተሰቅለው ከብደቱን ለማንሳት እንዲጠቅሙ ሆነው የተገጣጠመ ሙበት ከዋኝ

ማንሸረኛ Crane

በሞተር እየተንቀሳቀሰ ከባድ ነገሮችን ከቦታ ወደ ቦታ የሚያመላልስ ረዥም የብረታ ብረት መዋቅር

ማንጠር Demodulate

በተሸካሚ የራዲዮ ሞገድ አማካይነት የተላለፈን መልእክት ከተሸካሚው ለይቶ ማውጣት:: እንጥርት- Demodulation ፣ አንጣሪ- Demodulator

ማእከላዊ ሃይሎች Central forces

ከማናቸውም አቅጣጫ እየመጡ በአንድ ማእከል የሚያልፉ ሃይሎች

ማከፋፈያ ሰሌዳ Distribution board

የኤሌክትሪክ ሃይል በተለዋዋጭ ከረንቴ መልክ በሚከፋፈልበት ጊዜ የከፍፍሉን ሁኔታ መጠን የሚደላደልበትና ቁጥጥር የሚደረግበት ኤሌክዙር የያዘ ቦታ

ማቃደኛ Chuck

ልዩ ልዩ ቅርፅ እንዲወጣለት የተፈለገን ነገር ነክሶ ለመያዝ የሚያገለግል ባለተስተካካይ መንጋጋዎች አካል

ማውለቂያ Extractor

በሃይልገጥመት የተዋደደን ነገር ጉትቶ የሚያወጣ ከዋኝ

መዛነቅ Hetrodyne

ሁለት የተለያዩ ድግግሞሽ ያላቸውን የተለዋዋጭ ከረንቴ ሲግናሎችን በማደባለቅ የሁለቱን ድግግሞሾች ድምርና ልዩነት ድግግሞሾች ማውጣት

ማየተርቢ Hydraulic turbine

ውሃ ከከፍታ ቦታ ወደ ዝቅተኛ ሲፈስ የሚያገኘውን ጉልበት በኩላብ ዙረት ወደ መካኒካዊ ጉልበት መለወጫ መኪና

ማያያዝ Fastener

የመኪና ክፍሎችን የሚያስተሳስር ሊለያይና ላይለያይ የሚችል ነገር

መጻመጥ Rolling

ብረታ ብረቶችን በተሽከርካሪ ተንከባላዮች መካከል እየጻመጡ መጠናቸውን ማሳነስ / ተንከባላዮች = Rollers/

ማድከሚያ Dampener

በአንድ ነገር ላይ በድንገት የተከሰተን ውዝዋዜ በዝግታ የሚያስወግድ አካል

ማገጣጠሚያ ንድፍ Assembly drawing

የአንድ ነገር ልዩ ልዩ ተገጣጣሚ ክፍሎች እንዴት እንደሚገጣጠሙ የሚያሳይ አንጥ ንድፍ

ማጠናከሪያ ማንጠ Bracket

ለመደገፊያ ወይንም ለማጠናከሪያ እንዲያገለግል ከሌላ ነገር ጋር የሚገጠም አካል

ማፍሊያ Boiler

እንፋሎት ለማመንጨት የሚያገለግል የውሃ ማሞቂያ

ምላስ Blade (for rotors)

በታምቡር ዙሪያ በአንድ ጫፍ በኩል ተገናኝተው በፈሳሽር ሃይል ከታምቡሩ ጋር እየዞሩ መካኒካዊ አቅም ለመፍጠር፣ አየርን ለማሹቅ ወይንም አንዳንድ ነገሮችን ለመግፋት የሚያገለግሉ እንደምላስ ጠፍጣፋ ሆነው/ከአሸረት የተሰሩ አካላት

ምላጭ Blade (for cutting)

መሬትን ለመጥረብ በአፈር መገፊያ መኪና ላይ የሚገጠም ወይንም መጋዝ መሰል ማናቸውም አይነት መቁረጫ ወይንም መጥረቢያ

ምልስ ንዴት Back fire

በተለይ በቻበ ጫፍና በሞተር ውስጥ የሚፈጠረው ነበልባል ወደ ፊት መሄዱ ቀርቶ ወደአለ ተፈለገው ወደ ነዳጅ አቅጣጣይ ሲመለስ

ምራን ቀትርት Dowel

ሁለት ተጋጣሚ ገፀች በትክክል እንዲገጥሙ ለማድረግ በሁለቱ ገፀች ውስጥ በተበሱ ቀዳዳዎች የሚሰካ ጉጥ

ምስለክፋይ Cross section

አንድን ነገር ከምሸዋሩ ጋር 90° ባለው ጠላላ ሲቆረጥ የሚመስለውን የሚያሳይ ንድፍ

ምት Stroke

ተዘናዛኝ የመኪና አካል በእያንዳንዱ አቅጣጫ የሚያደርገው እንቅስቃሴ

ምንምን ስፍራ Depletion layer

ሁለት የተለያዩ ሙሌት ተሸካሚ ያላቸው ክፊል አስተላላፊዎች በሚጋጠሙበት ቦታ የሚፈጠር አነስተኛ ሙሌት ተሸካሚ ያለበት ጠባብ ስፍራ

ምንዝር Component

መመጪያች ያሉትና የራሱ የሆነ የኤሌክትሪክ ባህሪያት ኖሮት ከሌሎች ጋር በመገጠም አንድ የኤሌክዙርን ለመፍጠር የሚያስችል ክፍል:: ምሳሌ ጥንጥን፣ ትራንዚስተር፣ ከለ ወዘተ ...

ምንጪቃንቄ Spark plug

በውስጠቃጠሎ ሞተር ላይ በጥርስ አማካይነት በቀዳዳ ውስጥ ተገጥሞና ጧፏ ወደቤተቃጠሎ ብቅብሎ በኤሌክትሪክ አማካይነት እየሰራ ነዳጅንና አየርን የሚያቀጣጥል ከፃን

ረ

ረባዊ ከረንቲ/ቮልቴጅ/ Effective current (voltage)

በከል ውስጥ ሲያልፍ ከተመባበይ ቀጥተኛ ከረንቲ እኩል የሙቀት ሃይል ለመስጠት የሚችል የተለዋዋጭ ከረንቲ መጠን

ረከበት Chassis

እንደ ራዲዮ ያሉ የኤሌክትሮኒክ መሳሪያዎች ልዩ ልዩ ክፍሎች ተቀነባብረው የሚታሰሩበት እቃ

ሪግታ Capstan

ገመድ እየተጠመጠመበት ከባድ ነገሮችን ለመጎተት ወይንም ለማንሳት የሚያገለግል ተሽከርካሪ በርሜል መሰል መኪና

ራበድ Tetrode

ባለአራት መመጪ አየር አልባ ቀለህ ሲሆን አራተኛው ኤሌክትሮድ አጋጅ ይባላል

ርገኤሌክትሪክ Electrostatic

ተንቀሳቃሽ ያልሆኑ የኤሌክትሪክ ሙሌቶችን ባህሪይ ወይም ጠባይ የሚያመለክት

ሰ

ሰበቃዘዊ Angle of friction

አንድ ነገር በሌላው ላይ አርፍ እንዳለ ያንን ያረፈበትን ነገር በአንድ በኩል ቁና እንዲል ሲደረግ አላዩ የተቀመጠው ነገር መንሸራተት ሲጀምር ቢል የተከሰተው በግድምሽ ጠላላና በንኪኪያቸው ገፀታ መካከል ያለው ዘዊ

ሰነፍ ጥርስ Idler gear

በነጂና በተነጂ አንቀሳቃሽ ጥርሶች መካከል ተጠምዶ አቅጣጫቸውንና ፍጥነታቸውን ሳይለውጥ እንቅስቃሴን ለማስተላለፍ የሚረዳ አንቀሳቃሽ ጥርስ

ሰው መግቢያ Manhole

በርሜሎ፣ ማፍሌያ፣ ወይንም ጉርጓድ ወደመሳሰሉት ውስጥ ሰው እንዲገባበት ታቅዶ የተሰራ ቀዳዳ

ባለሰድ Triode

ባለሶስት መመጪ አየር አልባ ቀለህ ሆኖ ከክሲያድ ሁለት መመጪያች ሌላ አንድ መቆጣጠሪያ ኤሌክትሮድ ያለው

ሳጥና አገዳሚ Box girder

በአራት ማእዘን ወይንም በካሬ መልክ የተሰራ ውስጠ ክፍት አገዳሚ

ሴቴ ጥርስ ማውጫ አጀታ Die stock

ባለሁለት አጀታ የሴቴ ጥርስ ማውጫ ማቀፊያ

ስለቶዘዌ Angle of relief

በአዋዲ መኪና ላይ የሚሰካው መቀረጫ ጫፉ ከሚቀረፀው ነገር ጋር ፍትጊያ እንዳይኖረውና ለማቀበልም እንዲያመች የጫፉ ጉን ገፅታዎች ከሸቀብታ ጠለለ ጋር የሚኖራቸው ዘዌ

ስምረ ንድፍ/ የኤሌክዙር/ Diagram (circuit)

በአንድ ኤሌክዙር ውስጥ ልዩ ልዩ ምንዝሮቹ እንዴት እንደ ተያያዙ የሚያሳይ ስእላዊ መግለጫ

ስር Root

ጥርሶች ከዋናው አካል ጋር የሚገናኙበት ቦታ

ስስ Film

በጣም ስስ የሆነ የፈሳሽር ቅሽት

ስብራት Fracture

የአንድን ነገር የመሰበር ሁኔታ ወይንም ሂደት

ስብራት ጫና Breaking stress

አንድ ነገር ሲሳብ የብርታት ጫናውን ካለፈ በኋላ የሚሰበርበት አነስተኛ ጫና

ሰናግ ቀትርት Cotter pin

በቡሎን ውስጥ በመሸከት አሰሪው ከቡሎኑ እንዳይፈታ የሚያገለግል ወይንም በስክ ሙላ ውስጥ የሚያገለግል ሰንጥቅ ቀትርት /ስእል 10 ይመልከቱ/

ሰንብጥ አሰሪ Slotted nut

እናቱ ለሰናግ ቀትርት ማስተላለፊያ እንዲኖረው ተደርጎ የተሰራ አሰሪ /ስእል 11 ይመልከቱ/

ሶማ አስር Delta connection

በሶስት ማእዘን መልክ የተሰሩ የኤሌክትሪክ ጭነቶች ወይም ምንዝሮች ሆና በሶስቱ ጫፎች ከረንቴ የሚቀበል ወይም የሚያፈልቅ

## ሸ

ሸመኔ Chimney

በብረት፣ በጡብ ወይንም በሲሚንቶ የተሰራ ረጅም ውስጠክፍት ቋሚ የጭስ መውጫ

ሸርተቴ ኩሺኔታ Sliding bearing

ሁለት ብረቶች በፍትጊያ እየተፋጩ እንዳያልቁ የሚከላከል ለስላሳ የብረት ቱቦ ወይንም ለስላሳ የውስጥ ሽፋን ያለው የብረት ቱቦ፣ ቱቦው በቁመት ከሁለት የተከፈለ ሊሆን ይችላል

ሸከዛቢያ Arbor

በሸከርከርሽ ቀረፃ መኪና ውስጥ ሽከርከር ቆራጭን ወይንም የሚቆርፀውን ነገር የሚሸከም ኩላብ ወይንም ዘንግ

ሹሉን ጫና Yield point

አንድ ነገር በውጥረታዊ ጭነት ሲሳብ የልስትክነት ባህርዩን የሚያጣበት የጫና መጠን

ሸመለጌ Sleeve

በአንድ ነገር ላይ በመጠለቅ እንዲገጠም የተሰራ በርሜሉ መሰል ውስጠክፍት አካል

ሸርፍ Chamfer

አዲስ የተፈበረከ ነገር ጫፉ ወይንም ጠርዙ ለስለስ እንዲል ሰስላች የታፈፈ

ሽከርከር Wheel

ማና ቸውም ክብ የሆነና ለሽከረከር ወይንም ሊዘር የሚችል ክብቃ መሰል ነገር

ሽከርከር መሳል Grinding wheel

ሻከራ የሆነ ሽከርከር በመኪና ላይ ተገጥሞ ማንኛቸውንም ነገር ለመሞረድ የሚጠቀም

ሽከርከርሽ ቀረፃ Milling

አንድን ነገር መጠኑን ለማሳነስ ወይንም ለማስተካከል የሚደረግ መካኒካዊ ጠረባ

ቀ

ቀለም ኮድ Colour code

የአንድ ከለ መጠን ለማመልከት የሚረዳ የለዩ ለዩ ቀለማት አሰካክ ስርአት

ቀለበት Collar

ፊበሽር እንዳይተላለፍ ወይንም ረገቶ እንዲቆይ የተፈለገ ነገር በበታው እንዲቆይ ለማድረግ የሚያገለገል ጠፍጣፋ የቀለበት መልክ ያለው አካል

ቀላጭ / ቀላጭ ማረጋገጫ/ Fuse

አነስተኛ የተወሰነ ውፍረት ያለው ሽቦ ያለበትና ከተወሰነ ከረንቲ መጠን በላይ ሲያልፍበት በመቀለጥና በመበጠጥ ያለበትን የኤሌክዙር የሚከፍት የመሳሪያዎችን ደህንነት መጠበቂያ ከፃኝ:: ማንናውም የኤሌክትሪክ መሳሪያ በመለከም ሁኔታ ሲሰራ በውስጡ የሚያልፈው ከረንቲ መጠን የተወሰነ ነው:: በአንድ አጋጣሚ የዚሀ የተወሰነው ከረንቲ መጠን ከፍ ሲል በውስጡ ያለው ቀላጭ ስለሚበጠስ ከረንቲው ወዲያውኑ ስለሚቋረጥ መሳሪያው ከመበላሸት ይድናል:: የተበጠሰውን ቀላጭ መልሰ ለመጠቀም አይቻለም:

ቀረፃ Shaping

ብረታብረትን በተፈለገው መጠን ለማስተካከል ቆራጩ አካል በሚዘናዘን መኪና መጥረብ

ቀበቶ መፍቻ Strap wrench

በፍትጊያ ሊበላሹ የሚችሉ የመኪና ክፍሎችን ለማሰርና ለመፍታት የሚያገለግል ከቆዳ ወይም ከሸራ የተሰራ ቀበቶ መሰል አካልና የብረታብረት እጀታ ያለው ማቀላጠፊያ

ቀዛፊ Impeller

እንደ አራጋቢና አዙሪት ፓምፕ በመሳሰሉት ከዋኞች ውስጥ ተሽከርካሪው አካል

ቀዳሚ ማሞቂያ Preheater

በተለይ ፈሳሽሮች ካስፈለገም ጥጥር ነገሮች የመጀመሪያ ደረጃ ሙቀት እንዲያገኙ የሚያደርግ ሙቀት አለዋዋጭ ከዋኝ

ቀዳዳ Orifice

የፈሳሽርን ፍሰት ለመለካትና ለመቆጣጠር እንዲያገለግል ሆና የተሰራ የፈሽር መውጫ

ቀጥተኛ ከረንቲ Direct current

መጠኑ ከጊዜ ወደ ጊዜ የማይለዋወጥ ከረንቲ፤ ከባትሪ የሚገኘው ቀጥተኛ ከረንቲ ነው

ቀለፍ Key (machine)

በኩላብና በዷር መካከል ተቆርቆር አንፃራዊ ንቅናቄ ሳይኖር የሚያጣምዱ ትንሽ አካል /ስእል 12 ይመልከቱ/

ቁመት Length

የርዝመት መጠን

ቀምፀሬ Strain

በአንዱ ነገር ላይ በሚፈጠር የውጥረት ጫና በቁመት ላይ በሚያመጣው ለውጥ ሲካፈል የሚገኘው ውጤት

ቁጠባ ማሞቂያ Economizer

የተፈለገውን ስራ ካከናወነ በኋላ ሙቀቱ ሊባክን የሚችለው ወላፈን ሌላ ፈሳሽን እንዲያሞቅ የሚያደርግ አቃ

ቃንቄ ቃጠሎ Spark ignition

በውስጠ ቃጠሎ ሞተር ውስጥ የአየርና የነዳጅ ድብልቅ በምንጨ ቃንቄ አማካይነት ሲቀጣጠል

ቀሳንገት Funnel

ፈሳሽን ከአንዱ መያዣ ወደሌላው ማስተላለፊያ /ስእል 13 ይመልከቱ/

ቀምበቢት ጥርስ Bevel (cone) gear

ሁለት ኩላቦችን በመቀን ሊያገናኙና አቅም ሊያስተላልፉ ከሚችሉት እንቀሳቃሽ ጥርሶች አንዱ /ስእል 14 ይመልከቱ/

ቅርፅ ማውጫ Die

የተፈለገውን አይነት ቅርፅ ለማውጣት የሚያገለግል ቤተ ቅርፅ ወይንም ማቀላጠፊያ



14. ቀንበቢት ጥርሶች



15. ቁላበሪ



16. ቁላሬ ለደላዳይ



17. በር ከፍከቤ



18. ቡሎን



19. ባለዘንግ ክብ መስሪያ



20. ቡሎክ



22. ብይ ኩቢኔታ



23. ቧንቧ መፍቻ



24. ቨር ኒር ካሊበር

ቅርፅ ማውጫ Die
ብረታ ብረቶችን ወይንም ሽክላዎችን ቅርፅ እንዲወጡላቸው የሚያገለግል ማቀላጠፊያ ወይም ቢተቅርፅ

ቅስርነት Stiffness
አንዱ የማይለዋወጥ ሀይል በአንዱ ነገር ላይ ሲያርፍ በጥነቱና በተሸከሚው የቅርፅ መለወጥ መካከል ያለው ወደር

ቀስቃሴ.መሪ Guide
የመኪናን ተንቀሳቃሽ አካል ከተፈለገው መስመር ውጭ እንዳይወጣ የሚመራ ሌላ አካል

ቀሸላ Charging•
የኋለበት ምንጭ የሆነን ነገር ኋለበትን እንዲሰጥ ወደሚያደርገው በታ ማስገባት ወይንም ማጉረስ

ቀብ ሽቦ Enamelled wire
ቢዛነት ባለው ነገር የተቀባ ከረንቴ አስተላላፊ ሽቦ

ቀነቃ ቀደም ተከተል Firing order
በውስጠ ቃጠሎ ሞተር ውስጥ ምንጪቃንቄያች የሚሰሩበት ቀደም ተከተል

ቀይጥ Alloy
ከሁለት ወይንም ከሁለት በላይ የብረታብረት ንጥረ ነገሮች የተሰራና የብረታ ብረት ባህርይ ያለው ቅስ፣ ሁሉም ንጥረ ነገሮች ብረታብረት ላይሆኑ ይችላሉ

ቀይጥ ኤሌክዙር Hybrid circuit
አንዱ ወጥ የሆነ ኤሌክዙር ከበትን ምንዝሮች ጋር ተቀነባበር የተዘጋጀና የተወሰነ ተግባር ለማከናወን የሚችል ኤሌክዙር

ቀደመ ቃጠሎ Preignition
በምንጪቃንቄ በሚሰሩ ውስጠ ቃጠሎ ሞተሮች ውስጥ ምንጪቃንቄው ከመሰራቱ በፊት የሚከሰት ቀጥለት

ቀደመ ትንፈሳ Preexhaust
በዝንዛኔ በሚሰራ ውስጠ ቃጠሎ ሞተር ውስጥ ፈሳሽር ስራ ከስራ በኋላ ዝነዝነው ታችምት ከመድረሱ በፊት የጭስ መውጫትና ሂደት

ቀሻሰሪ / ቀላፊ አሰሪ/ Locknut
ከሌላ አሰሪ ጋር ተነባብሮ የሚታሰርና ሁለተኛው አሰሪ እንዳይፈታ ቀለፍ የሚይዝ /ስእል 15 ይመልከቱ/

ቀላፊ አደላዳይ Lock washer
ለዩ ለዩ ቅርፅ ሊኖረው የሚችል አሰሪን እንዳይፈታ የሚያደርግ አደላዳይ /ስእል 16 ይመልከቱ/

ቋር Hub
ጨከርከሮችና በከራዎች የመሰሰሉት ተሽከርካሪዎች ከኩላብ ጋር የሚገናኙበት ወፈር ያለ ማእከላዊ አካል

በ̈ራዱ ድም̈ሸት Cold rolling

ውፍረትን ለመቀነስና ገፅታን እያስተካከሉ ለማጠንከር ብረታብረትን በአከባቢው ባለው የአየር ሙቀት መዳመጥ

በርሜሉ Cylinder

በመካኒካል ምህንድስና ለዘነዘኔ መንቀሳቀሻ የሚሠ̈ራ ክብ ክፍተት

በር̈ ክፍክዱ Gate valve

ክብ ጠፍጣፋ መቆጣጠሪያ በቧንቧ ላይ ተገጥሞ ፍሰ̈ትን ለመቆጣጠር የሚያገለግል ከዋን /ስእል 17 ይመልከቱ/

በከራ Pulley

በኩላብ ላይ ተገጥሞ በልዩ ልዩ አይነት መቀነት አማካይነት እየተሾከረከረ፣ አቅም የሚያስተላልፍ ሽከርክር

ቡሎን Bolt

በመሰረቱ አጭር ዘንግ ሆኖ በአንዱ ጫፍ በኩል ባለ አራት ማእዘን ወይንም ባለ ስድስት ጐን ራስ ያለውና ዘንጉ ደግሞ በከፊል ወይንም ሙሉ በሙሉ ባለ ጥርስ የሆነ ነገሮችን ለማስተላለፍ የሚያገለግል አካል /ስእል 18 ይመልከቱ/

ባለአቅጣጫ አንቴና Directional antenna

በተወሰነ አቅጣጫ ለይቶ የራዲዮ ሞገድ ለማጥረር ወይም ለመቀበል የሚችል አንቴና

ባለዘንግ የእጅ ሞርሳ Bar clamp

ረጅም አሞሌና ተስተካካይ መንጋጋ ያለው ለአንጨት ስራ የሚያገለግል ቆንጣጭ ከዋን

ባለዘንግ ክብ መስሪያ Beam compass

የእርሳሱ ወይንም የምልክት መስሪያው መያዣ በረጅም አግዳሚ ዘንግ ላይ ለመንቀሳቀስ እንዲችል ሆኖ የተሰራለት ትልቅ ክብ መስሪያ /ስእል 19 ይመልከቱ/

ባለጥርስ ፓምፓ Gear pump

በሁለት የተጠመዱ ጥርሶች አማካይነት በእቃ ፈሳሽን ከአንዱ በኩል ወደሌላ የሚያስተላልፍ ከዋ̈ን

ባሮሜትር Barometer

በተለይ የከባቢ አየርን ግፊት ለመለካት የሚያገለግል ፍፁም ግፊት መለኪያ

ቤተቃጠሎ Combustion chamber

በውስጠ ቃጠሎ ሞተር በርሜሉ ውስጥ ከዘነዘኔ ራስ በላይ የሚገኘው አብዛኛው የቃጠሎ ሂደት የሚከናወንበት ክፍል

ቤተ ቅርፅ Mould

ተጠፍጣፊ የሆነን ነገር በውስጡ አቅፎ የራሱን የውስጥ መልክ ለታቃፊው የሚያስተላልፍ እንደሳጥን የተሰራ እቃ

ቬንቱሪ ቱቦ Venturi tube

በፍሰት መስመር ላይ በመገጠም የፈሳሽን ፍሰት ለመለካት የሚረዳ ወገበ ቀጭን አጠር ያለ ቱቦ:: በካርቡሬተርም ውስጥ በመሰረቱ በዚሁ መልክ ተደዝኖ የነዳጅ ዝብጥ ለመፍጠር ያገለግላል

ብሎክ Cylinder block

በዝንዝኔ በሚሰሩ ውስጥ ቃጠሎ ሞተሮች ውስጥ በርሚሎችን የሚይዘው ትልቅ ውስጥ ክፍት አካል /ስእል 20 ይመልከቱ/

ብረት ማፍረስ Casting

ብረታ ብረትን አቀለጠ ፈሳሹን ወደ ተወሰነ ቢ ተቀርፀ ውስጥ በማስገባት የተፈለገውን ቅርፅ ይዞ እንዲወጣ ማድረግ

ብሬተን ኡደት Brayton cycle

በሁለት ኢተለዋዋጭ አንትራቢ ሂደቶች የተገናኙ ሁለት ኢተለዋዋጭ ጬቃ ያሉበት የኡደት አይነት

ብርታት Strength

አንድ ነገር እመሰበር ወይንም እመድከም ደረጃ እስኪደርስ ድረስ ሊቋቋመው የሚችለው ጫና

ብርታት ጣራ Ultimate strength

አንድ ነገር ሲሳብ ሊቋቋመው የሚችለው ከፍተኛው የጫና መጠን

ብይኩሺኔታ Ball bearing

ብዙ የአረብረት ኳሶች በመካከላቸው የተገጠሙባቸው ሁለት ማእከለ አንድ ገጥምጥም የአረብረት ቀለበቶች:: ይህ ገጥምጥም በቋሚና በተንቀሳቃሽ የመኪና አካላት መካከል ተገጥሞ ፍትጊያን ነፁ በመቀነስ እንቅስቃሴ እንዲኖር የሚያስችል ነው:: /ስእል 22 ይመልከቱ/

ቦይ Groove

በጥጥር ነባር ገፅታ ላይ ጥልቀቱ አጭር ሆና የተሰራ ረጅምና ጠባብ ጎርጓዳ

ቧንቧ መፍቻ Pipe wrench

ቧንቧን አጥብቆ ይዞ በአንድ አቅጣጫ ብቻ ለመጠምዘዝና ለማዞር የሚያገለግል የእጅ ማቀላጠፊያ /ስእል 23 ይመልከቱ/

ፐ

ፐርኒር መለኪያ Vernier scale

የፐርኒር ካሊበር ክፍል የሆነና በማንሸራተት ረቂቅ የሆኑ የመጠን ክፍልፋዮችን ለኸቶ መጠናቸውን በአጥጋቢ ሁኔታ ለማንበብ የሚያስችል

ፐርኒር ካሊበር Vernier caliper

የውፍረት የውስጥ ስፋትና የጥልቀት መለኪያ /ስእል 24 ይመልከቱ/

ቪቴ Screw

ነገሮችን አብሮ አጥብቆ ለማሰር የሚያገለግል አሳሪ የለሽ ቡሎን /ስእል 25 ይመልከቱ/



25. ፒት



26. ተለዋዋጭ





27. ተሳሳሪ ሞሳ



28. ተሰኪ መፍቻ



34. አየር አለባ /ኢለክትር ኒክ/ ቀለህ



29. ተስ ተካካይ መፍቻ



30. ተቀባይ



31. ቴስ ታታ



32. አቻ ቁራጭ




33. አውዶ መስመሮች

ተ

ተለጠጣኪ Elastic

በ ሃይል ምክንያት የነበረውን ልክ የሚለቅና ሃይሉ ሲነሳለት ወዲያውኑ ወደ ቀድሞው ልክ የሚመለስ

ተለዋዋጭ ከረንቲ Alternating current

የከረንቲው መጠን ወይም የሚፈስበት አቅጣጫ በየጊዜዉ የሚለዋወጥ:: በየቤት የምንጠቀምበት የከረንቲ አይነት ተለዋዋጭ ሲሆን ለውጡም በስእሉ እንደተመለከተው ሳይናዊ መልክ አለው /ስእል 26 ይመልከቱ/

ተሳሳፊ ሙሌ Lap joint

ሁለት ነገሮችን ጫፋቸውን በማስተሳለፍ በቡሎን፣ በከምሱር ወይንም በበየዳ የተገናኙበት አካል /ስእል 27 ይመልከቱ/

ተራንደፍ Sketch

ትክክለኛ ልክን ሳይከተሉ እንጥንጥፍ አስመስሉ መንደፍ

ተሰኪ መፍቻ Socket wrench

በቡሎን ራስ ላይ ተሰክቶ ለመፍታት ወይንም ለማሰር የሚያገለግል የእጅ ማቀላጠፊያ /ስእል 28 ይመልከቱ/

ተስተካካይ መፍቻ Adjustable wrench

በተለያየ መጠን የተሰሩ ቡሎኖችን ወይንም አሳሪያቸ ለመፍታት ወይንም ለማሰር የሚያገለግል ተስተካካይ ማቀላጠፊያ /ስእል 29 ይመልከቱ/

ተቀባይ Collector

ከለቃቂው የሚወጡትን የኤሌክትሪክ ሙሌት ተሸካሚያቸን የሚቀበል የትራንዚስተር አንዱ ክፍል /ስእል 30 ይመልከቱ/

ተቃራኒ ግፊት Back pressure

ፈሳሽር ከአንዱ አቅጣጫ ወደሌላው ሲሄድ በሚያጋጥመው ተቃራኒ ሃይል ምክንያት የሚፈጠረው የሃል ዋጋ ግፊት

ተቃቃፊ ሙሌ Knuckle joint

ሁለት ዘንጎች በቅትርት የተገናኙበት አካል

ተቆጣጣሪ Governor

በሚሽከረከሩ ክብደቶች አማካይነት አየተንቀሳቀሰ የመኪናን ፍጥነት ወይም አቅም ለመቆጣጠር የሚያገለግል ክፍል

ተቆጣጣሪ አንቀሳቃሽ ጥርሶች Timing gears

በዝንዝኒ በሚሰራ ሞተር ውስጥ የመዘወሪያና የወለፈንዲ ኩሳቦችን ፍጥነት በተፈለገው መጠን የሚያዘምዱ ሰሰፈአንቀሳቃሽ ጥርስ

ተቆጣጣሪ ወንፊት Control grid

በአየር አልባ ቀለህ ውስጥ ከካቶዱ የሚለቀቁትን ኤሌክትሮኖች ለመቆጣጠር የሚያስችል አብዛኛውን ጊዜ እንደ መረብ የተሰራው ክፍል

ተቋራኝ አቃቤሌክትሪክ Gangeo capacitors

በአንድ ዘንግ ላይ የተሰሩ ሁለት ወይም ከዚያ በላይ የሆኑ፣ መጠናቸው ዘንጉን በማዞር አንድነት ሊለዋወጥ የሚችል አቃቤሌክትሪኮች

ተን መሻሽ Condenser

ማናቸውንም ተን ወደ ፈሳሽነት የሚለውጥ ሙቀት አለዋዋጭ

ተንማጋያ Superheater

በተን ውስጥ ሊገኝ የሚችለውን ፈሳሽ እያተነነ ተኑ የበለጠ እንዲደርቅና እንዲግል የሚያደርግ የተጣመረ ቱብ

ተንሸራታች ክፍክድ Slide valve

ፈሳሸር እንዲገባ ወይንም እንዲወጣ ለማድረግ በፈሳሸሩ በር ላይ እየተንሸራተተ ጊዜ ጠብቆ የሚዘጋና የሚከፍት ክፍክድ

ተን አምፑል Discharge lamp

በአንድ መያዣ /አብዛኛውን ጊዜ መስታወትነት ያለው/ ውስጥ በሁለት ኤሌክትሮዶች በመሀከል ባለው ዝቅተኛ ግፊት ያለው ተን ውስጥ ከረንት በማስተላለፍ ብርሃን የሚሰጥ አምፑል/አሸብራቂ አምፑልን ተመልከት/

ተዘናዛኝ ሞተር Reciprocating engine

ዘነዘኔ በበርሜሉ ውስጥ ሆኖ እየተዘናዘነ የሚሰራበት የሞተር አይነት

ተደራራቢ ሙላ Strap joint

ሁለት ጠፍጣፋ ብረታብረቶችን ሳይገናኙ በሁለቱም ገፃቸው በኩል ሌሎች ጠፍጣፋ ብረታብረቶች በመደራረብ በብየዳ፣ በቡሎን ወይም በከምሱር የተገናኙበት አካል

ተጋብ ቮልቴጅ Induced voltage

አንድ አስተላላፊ በተለዋዋጭ ማግኔታዊ አውድ ውስጥ ሲኖር ወይም ይህ አስተላላፊ በማግኔታዊ አውድ ውስጥ ቢንቀሳቀስ፣ በአስተላላፊው ሁለት ጫፎች መካከል የሚፈጠረው ቮልቴጅ

ተጋቦት ጥንጥን Induction coil

አነስተኛ መጠን ካለው ቀጥተኛ ከረንት ከፍተኛ የሆነ ተለዋዋጭ ከረንት ወይም ከፍተኛ የትርታ ቮልቴጅ ለማውጣት የሚችል የጥንጥን ቀንበር/ማቀጣጠያ ጥንጥን ተመልከት/

ተጠሪ መጠን Nominal size

እጅግ በጣም ትንሽ የሆነን ልዩነት ሳይጨምር የአንዱን ነገር መጠን በቀላሉ የሚያሳይ አሃዝ

ተጠፍጣፊ Malleable

ወደ ተፈለገው ቅርፅ ለመለወጥ የሚችል ታዛዥ የሆነ ነገር

ቱብሽ መፍቻ Tube wrench

አጠቃላይ መልኩ የአጭር ቱብ ሆኖ በሁለቱም ጫፎች የቡሎን ራስ አቅፍ ይዘ ቡሎኑን ሊያሰር ወይም ሊፈታ የሚችል መፍቻ

ታቃፊ ኩሳብ Journal

በኩቺኒታ ውስጥ ተገጥሞ የሚሽከረከር የኩሳብ ወይንም የመዘወሪያ ኩሳብ ክፍል

ታች መቆሚያ Botton dead center

በዝንዛኔ የሚሰራ ሞተር፣ አማቂ ወይንም ፖምፓ ውስጥ ዘነዘኔው ልክ የታች ምቱን ሲጨርስ የመዘወሪያው ኩሳብ ያለበት ቦታ

ታችሜዳ Botton land

በአንቀሳቃሽ ጥርስ ላይ በየሁለት ጥርሶች መካከል በሚገኘው ክፍተት ውስጥ ዝቅተኛ ቦታ

ታች ክፍክፍ Foot valve

ፖምፓ ፈሳሽን ከሚስብበት በኩል ከፈሳሹ ውስጥ ሆኖ ፈሳሹ ወደሁዋላ እንዳይ መለስ የሚያደርግ ክፍክፉ

ቱስ ታታ Cylinder head

በዝንዛኔ በሚሰሩ ውስጥ ቃጠሎ ሞተሮች፣ አማቂያች ወይንም ፖምፓያች ውስጥ በርሜሎችን በዘነዘኔው ራስ በኩል የሚዘጋ አካል /ስአል 31 ይመለከቱ/

ትራንዚስተር Transistor

ከከፊል አስተላላፊ ጥጥር የሚሰራ ባለሶስት መመጪ የኤሌክትሮኒክ ክፍን ሲሆን አብዛኛውን ጊዜ የኤሌክትሮኒክ አግናኝ ለመስሪያ ይውላል

ቸ

ቺንጊያ V-belt

ጠርዙ የእንግሊዝኛውን ፊደል V ን በሚመስል መልክ በተቀረፀ በከራ ላይ ተገጥሞ አቅም የሚያስተላልፍ ክብ መቀነት

ችቦ Torch

ነዳጅአየር እያነደደ ብረታ ብረትን ለማሞቅ፣ ለመቁረጥ ወይንም ለመበየድ የሚያገለግል ማቀላጠፊያ

ነ

ነጥበ ቃጠሎ Flash

ከፈሳሽ ነዳጅ ላይ የሚነሳ ተን በትንሽ ነበልባል አማካኝነት የሚቀጣጠልበት የመጨረሻው ዝቅተኛ ሙቀት ልክ

ንዴት Combustion

ማናቸውም አይነት ነዳጅ ከአክስጅን ጋር በመዋሀድ እየተቃጠለ ነበልባል ወይንም ፍም በማሳየት ሙቀት ሲሰጥ

ንፀረ እሙቃ Compression ratio

የውስጠ ቃጠሎ ሞተር ዘነዘኔ ራስ የእመቃ ሂደት ከሚጀምርበት ቦታ በላይ ያለው ጠቅላላ የበርሜሉ ይዘት ከላይኛው መቆሚያ በላይ ካለው ይዘት ጋር ሲወዳደር የሚገኘው የማወዳደሪያ ቁጥር

አሃዛዊ Digital

በተወሰነ ጊዜ ውስጥ የተወሰነ መጠን ኖርት በተከታታይ የሚከሰትና ከሚወክለው ፊዚካዊ ነገር ጋር አምሳያዊነት የሌለው:: በማይክሮፎን አማካኝነት ወደ ኤሌክትሪክ የሚለወጥ ድምፅ ከማይክሮፎኑ ሲወጣ አምሳያ ቢሆንም ይህንኑ አሃዛዊ ለማድረግ ይቻላል

አሳባ Efficiency

አንድ ከዋኝ ወይም አቃ በሚሰራበት ጊዜ የወጭው ሃይል ከገቢው ጋር በመቶኛ ማነፃፀሪያ

አሙሳሳሸ Conveyor

ፈሳሸር ያልሆኑ ነገሮችን ከአንድ ቦታ ወደ ሌላው ያለማቋረጥ የሚያመ.ጓለስ አቃ

አማቂ Compressor

ጋዝን ወይንም ተንን በማመቅ ግፊት እንዲጨምር የሚያደርግ መኪና

አምሳያ Analog

አንድ ፊዚካዊ መጠን / quantity / የራሱን ምጥነት ሳይለውጥ በሌላ አይነት መጠን ሲታይ:: ሙቀት አምሳያው በሆነ የከረንቲ መጠን ሊለካ ይችላል:: አምሳያዊ የሆነ ኤሌክዙር የተቀበለውን ሲግናል መልኩንና ሌላ መሰረታዊ ጠባዩችን ሳይለውጥ የሚያስተላልፍ ወይም የሚጠቀምበት ነው:: /አሃዛዊን ተመልከት/

አረብረት Steel

በመሰረቱ ብረት ሆኖ እንደአስፈላጊነቱ ሌሎች ብረታብረቶች የተቀየጡበትና እስከ 2 በመቶ ከሰል ያለበት

አራትምት ሞተር Four stroke engine

በአራት ዝንዝኔ ምት በሚፈፀም ሱደት የሚሰራ ውስጠ ቃጠሎ ሞተር

አራጋቢ Fan

የማይፈለግ ጋዝ እንዲወገድ ወይም ንፁህ አየር በተፈለገው ቦታ እንዲዘዋወር የሚያገለግል ባለሸክርክር ከዋኝ

አራጋቢ መቀነት Fan belt

አቅምን ከአንድ በከራ ወደሌላው በማስተላለፍ አራጋቢን ለመንዳት የሚያገለግል ክብ መቀነት

አርብ Width

የአንድ ነገር የጎን ልክ

አስር ዎሽ ሳጥን Decade box

የተያያዙ ከሎች ወይም አቃቢሌክትሪኮች ወይም ጥንጥኖች በሳጥን ውስጥ የተቀናጁና መጠናቸውን በአስር ብዜቶች ወይም በአስር ክፋዮች ከፍና ዝቅ ለማድረግ የሚቻልበት አቃ

አስተላላፊ Conductor

የኤሌክትሪክ ከረንትን ለማስተላለፍ የሚችል

አስተላላፊያዊ Conductance

አስተላላፊያዊነት Conductivity

አስተላላፊነት Conduction

አቃቢሌክትሪክ Capacitor

በቢዝ ከተለያዩ ሁለት ኤሌክትሪክ አስተላላፊዎች የሚሰራ የኤሌክትሪክ ከዋኝ ሲሆን ቀጥተኛ ከረንትን የማገዱ፣ ተለዋዋጭ ከረንትን የሚያስተላልፍና የኤሌክትሪክ ሃይልን የመያዝና የማጠራቀም ችሎታ ያለው

አቃቢሌክትሪክነት Capacitance

አቃ‾ Rectifier

በአንዱ አቅጣጫ ብቻ ከረንትን ለማስተላለፍ የሚያስችል የኤሌክትሪክ ዙር ምንዝር፡፡ ሳይናዊ የኤሌክትሪክ ሲግናል ተቀብሎ አሉታውን በማስቀረት አወንታውን ብቻ የሚያስተላልፍ ምንዝር የአቃኝ አንዱ ምሳሌ ነው፡፡ የከፊል አስተላላፊ ወይም የአየር አልባ ከለያይ የዚህ ምንዝር አንዱ ምሳሌ ነው

ቅኝት Rectification

ሙሉ ቅኝት Full-wave rectification

ግማሽ ቅኝት Half-wave rectification

የተቃኘ /ከረንት/ Rectified (current, .....)

አቅፍ አሰሪ Clamp

ልዩ ልዩ ነገሮችን በተፈለገው ሁኔታ ለአጭር ወይም ለረጅም ጊዜ ተጭኖ አብሮ ለመያዝ የሚያገለግል መቆንጠጫ ወይም ማሰሪያ

አባሪ ውጤት By-product

ምርት ሲመረት ከሚፈለገው ምርት ሌላ አብሮ የሚወጣ ነገር

አብራጅ Coolant

ሙቀት የሚያመነጭን መኪና በተወሰነ መጠን የሚያቀዘቅዝ ፈሳሽ

አቻቀራጭ Countersink

የመሰርሰሪያ ጫፍ አካል ሆኖ በእሱ አማካይነት የሚበሳው ቀዳዳ የራሱን ቅርፅ የሚመስል ሌላ አካል በትክክል እንዲገጥም አድርጎ የሚቀርፅ /ስእል 32 ይመልከቱ/

አኖድ Anode (plate)

1/ የባትሪ ዱንጋይ ወይም የባትሪ አወንታ መመጪ / terminal /

2/ በአየር አልባ ቀለህ ውስጥ ኤሌክትሮኖችን የመሰብሰብ ችሎታ ያለው አንዱ ክፍል

3/ የከፊል አስተላላፊ ከለያይ አንዱ መመጪ ሆኖ ከለያዩ ወደፊት በሚዝምበት ጊዜ ከረንቱ ወደ እሱ የሚፈስበት ጫፍ ነው

**አቾነት** Toughness

አንድ ነገር ሃይል ሲያርፍበት ሰንጥቅ ሳያሳይ ቅርፁም ቢለወጥ ሳይሰበር ያረፈበትን ጫና ለመቋቋም ያለው ችሎታ።

**አከናፊ** Propeller

በኩሳብ ጫፍ ላይ ተገጥሞ እየተሽከረከረ በኩሳቡ አቅጣጫ ገፊት እየፈጠረ የሚነዳ ፏሪቲ መሰሰ ከዋኝ

**አውራ ቀትርት** Kingpin

እያንዳንዱ የተሽከርካሪ የፊት ጎማ ከፍሬኑ ገጥምጥም ጋር በመሪ አማካይነት የሚዟዟርበት የሙሳ ቀትርት

**አውድ መስመሮች** Field Lines

የአንዱን አውድ ጥንካሬ ለማሳየት የሚሳሉ የሀሳብ መስመሮች:: የአውድ ጥንካሬ መጠን ከፍተኛ በሚሆንበት ስፍራ መስመሮቹ የተጠጋጉ ሲሆኑ አነስተኛ የአውድ መጠን በሚኖርበት ስፍራ ደግሞ መስመሮቹ ምንምን ይሆናሉ:: በሁለት የማግኔት ዋልታዎች መሀከል ባለው ስፍራ የሚኖረትን የማግኔታዊ አውድ መስመሮች /ስእል 33 ይመልከቱ/

**አዙሪት ለዩ** Centrifuge

ልዩ ልዩ አፍጋት ያላቸው ፈሳሾች ወይንም የቾቾርና የፈሳሽ ድብልቅ በአዙሪት ሃይል እንዲለያዩ የሚያደርግ ከዋኝ

**አዙሪት ፖምፖ** Centrifugal pump

አንድ ቀዛፊ በቀፎ ውስጥ ሆኖ እየተሽከረከረ በአዙሪት ሃይል ውሃን ወይንም ሌላ አይነት ፈሳሽን ከአንድ ቦታ ወደ ሌላ ቦታ የሚያስተላልፍ

**አዛናፊ ጥንጥን** Deflection coil

በአሲሎስኮፕ ወይም ሌላ እቃ ውስጥ የኤሌክትሮኖችን ጨረር ወደ ላይና ታች ወይም ወደ ጎን ለማንቀሳቀስ የሚረዳ

**አዛይ** Carrier

በራድዮ የመገናኛ ዘዴ ውስጥ ተፈላጊውን መልእክት ተሸካሚ የሆነ አብዛኛውን ጊዜ ከፍተኛ ድግግሞሽ ያለው የኤሌክትሪክ ሲግናል

**አዠጋሚ** Dashpot

እንቅስቃሴን እየተቆጣጠረ እንዳይፈጥን የሚያደርግ ከዋኝ

**አዝማሚ/ማዝመሚያ/** Bias

የተፈለገውን የአሰራር ሁኔታ ለማስገኘት ወይም ለማስፈን ለትራንዚስተር ወይም ለአየር አሰቢ ቀለሀ መመጧያች የሚሰጥ የቀጥተኛ ከረንቲ ሸለቴጅ

**አየር መስማማት** Air conditioning

አንድ የተወሰነ አካባቢ ወይንም ቦታ ለተፈለገ ተግባር እንዲስማማ የአየሩን ሙቀት፣ ፍሰት፣ ርጥበት ወዘተ መቆጣጠር

**አየር አልባ /ኤሌክትሮኒክ/ ቀለሀ** Vacuum (electronic) tube
የኤሌክትሪክ ሲግናልን መጠን፣ መልክና ሌሎች ባህሪያትን ለመለዋወጥ የሚያስችል ከዋኝ:: ቀለሁ ሁለት ወይም ከዚህ በላይ ኤሌክትሮዶች ሊኖሩት ይችላል /ከል ያድ፣ ባለሰድ፣ ራበድ ወዘተ ... ተመልከት/ /ስእል 34 ይመልከቱ/

**አያያዥ** Connector
ሁለት የኤሌክትሪክ ምንዝሮችን ወይም ዙሮች ለማያያዝ የሚጠቀም እቃ

**አይመለሴ ክፍክፍ** Non-return Valve
ፈሳሽ በአንድ አቅጣጫ ብቻ እንዲፈስና እንዳይመለስ የሚያደርግ ክፍክፍ

**አይነበጎ** Hole
በጠጣር ክፈል አስተላላፊ ነገር ውስጥ ኤሌክትሮን በታውን ለቆ ከስቶ ሲለይ የሚፈጠር ሁኔታ:: አይነበጎ የአወንታ ሙሌት ተሸካሚ ደቂቅ ጠባይ አለው

**አደላዳይ** Washer
አሰሪ በብሎን ላይ ተገጥሞ ሲጠበቅ በታሰሪው አካል ላይ የሚፈጠረው ጫና ሰፋ ባለ ቦታ ላይ እንዲከፋፈልና አሰሪውም እንዳይፈታ የሚያደርግ ጠፍጣፋ ቀለበት መሰል ከብረታብረት የተሰራ አካል /ስእል 35 ይመልከቱ/

**አዳቢ** Adiabatic
የሙቀት መተላለፍ የማይከሰትበት ማናቸውም አይነት ሂደት

**አገናኝ ዘንግ** Connecting rod
የዘንዥነን እንቅስቃሴ ወደ ዙሮሽ ወይንም የዙሮሽን ወደ ዘንዥነ የሚለውጥ በሁለት ባለቀትርት ሙሳያች መካከል የሚገኝ ዘንግ /ስእል 36 ይመልከቱ/

**አገናኝ** Amplifier
አነስተኛ መጠን ያለውን ተለዋዋጭ ከረንቲ ተቀብሎ መልኩን ሳይለውጥ የልከር ግብግብታ መጠኑን ወይም ጉልበቱን ከፍ ለማድረግ የሚችል ከዋኝ ወይም እቃ:: ለምሳሌ ማንኛውም ራዲዮ በአንቴናው በኩል የሚቀበለውን በጣም ዝቅተኛ መጠን ያለውን ሞገድ ወደ ድምፅ ከመለወጡ በፊት በተከታታይ በተያያዙ የኤሌክትሮኒክ አገናኞች መጠኑን ከፍ ያደርጋል

**አጥላይ /የኤሌክትሪክ/** Filter (electric)
ከገቢ የኤሌክትሪክ ሲግናሎች የተወሰኑ ድግግሞሽን ብቻ መርጦ ለማስተላለፍ የሚችል የኤሌክትሪክ መረብ

**አፈሙዝ** Nozzle
ፈሳሽር አንድ አቅጣጫ ይዘ ግፊቱን እየቀነሰ በፍጥነት እንዲፈስ የሚያደርግ አጭር ቱብ መሰል ከዋኝ

**ኡደት** Cycle
ተለዋዋጭ ከረንቲ ከተወሰነ መጠን ተነስቶ ሙሉ ዙር ካደረገ በኋላ እዚያ የሚመለስበት ሁኔታ /ስእል 37 ይመልከቱ/



35. አደላዳይ



36. አገናኝ ዘንግ



37. ኡደት



38. አባጨከርከር



39. አብር መግቢያ



40. አብር ጭስ መውጫ



41. አንከብል ኩሽኔታ



42. አንጨት መሰርሰሪያ



43. ጉባጤ



45. ከምሱር



46. ከንፈር



47. ኩርባ ማስመሪያ

ኢግለጠት Interference

አንድ ተሰኪ ወደሚሰካበት ቀዳዳ ሲገባ ሰተት ብሎ እንዳይገባ የሚያገደው የተሰኪው የመጠን ብልጫ

ኤሌክትሪክ ብልጭታ Electric spark

በሁለት ኤሌክትሮዶች መሀል ያለው የቮልቴጅ መጠን ከፍተኛ ሲሆን በመሃከላቸው ያለው አየር ወይም ሌላ ቢዛ ለአጭር ጊዜ ከረንቲ ሲያስተላልፍ የሚታየው ቀፀ በታዊ ብልጭታ ነው:: የመብረቅ ብልጭታ አንድ ምሳሌ ነው

ኤሌክትሪክ አውድ Electric field

የተንቀሳቃሽ ወይም የርግ የኤሌክትሪክ ሙሌቶች መሰረታዊ ባህሪይ ነው:: የኤሌክትሪክ ሙሌቶች በአሉበት አካባቢ የኤሌክትሪክ አውድ የሚፈጠር ሲሆን ይህም በሌሎች የኤሌክትሪክ ሙሌቶች ላይ ገፊትን ወይም ስበትን ሊያስከትል የሚችል ነው

ኤሌክትሪክ ጭነት Electrical load

ከአንድ የኤሌክትሪክ ማመንጫ ወይም ሌላ የኤሌክትሪክ ከምንጭ የሚወጣውን ሃይል የሚቀበልና የተወሰነ ተግባር የሚያከናውን እቃ

ኤሌክቶር ማግኔት Electromagnet

በብረት ላይ በተጠመጠመ አስተላላፊ ሽቦ ውስጥ ከረንቲ ሲያልፍ ብረቱ የማግኔትነት ጠባይ ይኖረዋል

ኤሌክትሮን Electron

የአሉታ የሌሌክትሪክ ሙሌት ተሸካሚ የሆነ የማንኛውም አቶም አካል የሆነ ደቂቅ አካል

ኤሌክትሮን ጨራ Electron beam

ከአንድ የኤሌክትሮን ለቃቂ አካል የሚወጡትን ኤሌክትሮኖች በተለያዩ ዘዴዎች አንድ መስመር ይዘው ሲጓዙ የሚፈጠር:: በቴሌቪዥን መቀበያ መስታወት ላይ የሚፈጠረው ብርሃን በኤሌክትሮን ጨራ አማካይነት ነው

ኤሌክዙር Circuit (electric)

ልዩ ልዩ የኤሌክትሪክ ምንዝሮች በማስተላለፊያ ሽቦዎች ተሳስረው ከረንቲን የሚያስተላልፍ ገጥም ዙር የሆነ

ኤሌክዙር ሰሌዳ Circuit board

የኤሌክዙር የሚጠላለፍበትና የሚሰራበት ሰሌዳ

እመቃ ቃጠሎ Compression ignition

በዲዘል ሞተር ውስጥ በታመቀ የአየር ሙቀት አማካኝነት የነዳጅ መቀጣጠል

አርገብጭራ ስክ Dovetail joint

የሴቷና የወንዱው ቅርፅ የእርገብ ጭራ የሚመስል ስክ

እባብሽክርክር Worm wheel

በጠርዙ ዙሪያ ከእባቡ ጋር እንዲገጥም ሆኖ የተቀረፀና ከእባቡው ጋር ሲጣመድ ምሷራቸው በ90° በሚተላለፉ ኩላቦች መካከል አቅም ለማስተላለፍ የሚችል ክብቃ /ስእል 38 ይመልከቱ/

ኡኒየን Union (joint)

በሁለቱም ጫፎች ላይ ጥርስ ወጥቶለት የሴጥር ቱቦና የአሰራሮች ገጥም ጥም የሆነ ሁለት ቱቦዎችን የሚያገናኝ የሙሌ አይነት

ኡኒየን መግቢያ Inlet manifold

በውስጠ ቃጠሎ ሞተር ውስጥ አየር ወይም የአየርና ነዳጅ ደብልቅ ወደ በርሜሎች የሚተላለፍበት ልዩ ቱቦ /ስእል 39 ይመልከቱ/

ኡኒየን ጭስ ማውጫ Exhaust manifold

በውስጠ ቃጠሎ ሞተር ውስጥ ከያንዳንዱ ጭስ መውጫ ከፍከይ ጭስ እየተቀበለ በአንድነት የሚያሰልፍ አካል /ስእል 40 ይመልከቱ/

ኡቶን Furnace

ፈሳሽን ወይንም ጥጥርን የኬሚካል ወይንም የቀርፀ ለውጥ እንዲያመጣ የሚያገለግል ማጋያ

እንክብልኩሽኒታ Roller bearing

በሁለት ማእከለአንድ ቀለበት ብረቶች መካከል ተንገሽ በርሚሏዊ ወይንም ሽጠጥ ያሉ ብረቶች ያሉበትና በሁለት የመኪና ክፍሎች መካከል ተገጥሞ ፍትጊያን በማሳነስ ነፃ ዙሪት የሚፈቅድ /ስእል 41 ይመልከቱ/

እንጥ ንድፍ Technical drawing

በትክክል እየተለከና እየተሰመረ የሚሰራ ስእላዊ መግለጫ

እንጨት መሰርሰሪያ Brace bit

በእጅ መዘወሪያ ጫፍ ላይ ተገጥሞ እንጨት ለመበሻ የምታገለግል ልዩ መሰርሰሪያ /ስእል 42 ይመልከቱ/

እንፋሎት ተርባ Steam turbine

የእንፋሎትን ጉልበት በሙላብ ዙረት ወደ መካኒካዊ ጉልበት የሚለውጥ መኪና

ኑባጤ Elbow

ሁለት ቧንቧዎችን በተፈለገው ዘዌ የሚያገናኝ ባለጥርስ ሙሳ /ስእል 43 ይመልከቱ/

አቶማቲክ መፍቻ Automatic wrench

ቡሎኖችን ወ'ንም አሰራዎችን ለማሰርም ሆነ ለማጥበቅ ከተገሙ በሃላ ሰይለ ቆቆ ለመፍታት ወይንም ለማሰር የሚያስችል መካኒዝም ያለው መፍቻ

ኦቶ ኡደት Otto cycle

ሁለት ኢተለዋዋጭ እንትረቢ ሂደቶች በሁለት ኢተለዋዋጭ ይዘት ሂደቶች የሚገናኙበት የኡደት አይነት

ከ

ከምሱር Rivet

ሁለት አካሎችን ለማያያዝ የሚያገለግል አጭር ቀጭን ምስማር መሰል ጠፍጣፋ ቀትርት /ስእል 45 ይመልከቱ/

**ከባቢ መፍቻ** Ring spanner
በቡሎን ራስ ላይ ከቦ በመስካት ቡሎኑን ለመፍታት ወይም ለማሰር የሚያገለግል ማቀላጠፊያ

**ከንፈራም ማቀናኛ** Flanged coupling
ሁለት ኩላቦችን ለማቀናጀት የሚያገለግል የሁለት ጠፍጣፋ የብረት ቀለበቶችና ቡሎኖች ገጥምጥም

**ከንፈር** Flange
ቱቦዎችንና ጋኖችን ለማገናኘት ወይንም ለመከደን የሚያገለግል ከንፈር መሰል አካል /ስእል 46 ይመልከቱ/

**ከፍተኛ ድግግሞሽ /ከድ/** High frequency (HF)
የድግግሞሹ መጠን ከሶስት ሚሊዮን /ሜጋ/ ኸርትስ እስከ ሰላሳ ሚሊዮን ኸርትስ የሆነ:: በራዲዮ ስራ አጭር ሞገድ ተብሎ ይጠራል

**ከፍተኛ ድግግሞሽ አጥላይ** High-pass filter
ከፍተኛ ድግግሞሽ ያላቸውን ሲግናሎች ለማስተላለፍ የሚችል አጥላይ

**ከፍታ** Height
ከአንድ መነሻ ጠለል እስከተፈለገው ቁመት

**ኩላቢት** Spindle (in general)
አጠርና ዘለግ ያለች ውስጠክፍት ወይም ቀምበብ ኩላብ

**ኩላብ** Shaft
ጥርሶችንና በከራዎችን ከመሳሰሉ የመኪና አካላት ጋር ተዋዶደ በመሽከርከር አቅምን የሚያስተላልፍ በርሚላዊ ብረታብረት ወይም አረብረት

**ኩርባ** Curve
ቀጥታ ያልሆነና ጠምዘዝ እያለ ዘዌ ሳይሰራ አቅጣጫ እየለወጠ የሚሄድ ማናቸውም መስመር

**ኩርባ ማስመሪያ** French Curve
ልዩ ልዩ ጎባጣ መስመሮች ለመስራት የሚጠቀም ለአንጥ ንድፍ ስራ የሚያገለግል ልዩ ማስመሪያ /ስእል 47 ይመልከቱ/

**ኩዳ** Nipple (grease)
ኩቺኔታ በአቃፊ አካል ላይ በጥርስ አማካይነት ተገጥሞ ቅባት ወደኩቺኔታው እንዲገባ በተፈለገ ጊዜ ለማስተላለፍ የሚያገለግልና አቧራም እንዳይገባ በልዩ ክፍከድ የሚከላከል በጣም አጭር የጡት ጫፍ መሰል ቱቦ

**ካርኖ ኡደት** Carnot cycle
በሁለት ኢተለዋዋጭ አንትራቢ ሂደቶች የተገናኙ ሁለት ኢተለዋዋጭ ሙቀት ሂደቶች ያሉበት የኡደት አይነት

**ካቡሬተር** Carburettor
በቤንዚን መኪናዎች ውስጥ ነዳጅንና አየርን በሚፈለገው መጠንና ወደር የሚያደባልቅ ከዋን

ከበ Cable

በርከት ያሉ የተባዙ ኤሌክትሪክ አስተላላፊ ሽቦዎች በአንድነት በአንድ ከፍተኛ ቢዛነት ባለው ቱቦ ውስጥ የታቀፉ:: ምሳሌ የቴሌፎን ከበ

ካቶድ Cathode

1/ የባትሪ አሉታ መመጪ

2/ በአየር አልባ ቀለሀ ውስጥ መደበኛው የኤሌክትሮኖች መፍለቂያ የሆነው አንድ ክፍል

3/ የከፊል አስተላላፊ ክልዮድ አንዱ መመጪ ሆኖ ክልዮዱ ወደ ፊት በሚዝምበት ጊዜ ከሌላው መመጪ ጋር ሲነፃፀር አሉታ የሚሆነው

ኬላ Gate

1/ ብዛት ያላቸው ገቢዎች ያሉትና በገቢዎች ትርታዎች መሃከል የተወሰነ ቅንብር ሲኖር አንድ ወይም ከዚያ በላይ ወጭ የሚሰጥ የኤሌክዙር

2/ የባለአውዱ ትራንዚስተር አንዱ መመጪ

የወያ ኬላ Exclusive or Gate

ወያ ኬላ Or gate

አጣማሪ ኬላ And gate

ክልል ስፋት Band width

ተፈላጊ ወይም ጠቃሚ የሆኑ የአንዱ የኤሌክትሪክ ሲግናል ድግግሞሾች የሚገኙበት ክልል ሲሆን መጠኑም በከፍተኛውና በዝቅተኛው የክልሉ ድንበር ድግግሞሾች መካከል ያለው ልዩነት ነው

ክልል ድግግሞሽ አጥላይ Band-Pass filter

በሁለት ድግግሞሽ መካከል ያሉትን ሲግናሎች ብቻ ለማስተላለፍ የሚችል አጥላይ

ክልሰና Calcination

አፈር ብረቶችን በማሞቅ ውሃንና ካርቦን ዳይአክሰይድን እንዲወጡ ማድረግ

ክልታ Hoe

ለአትክልት መኮትኮቻ የሚያገለግል የብረቱ አካል አካፋ የሚመስል ከዛቢያው ጋር እንደዶማ የተዋደደ ማቀላጠፊያ

ክልዮድ Diode

ባለሁለት መመጪ/ጪፍ/ የሆነ አየር አልባ ቀለሀ ወይም ከከፊል አስተላላፊ የሚሰራ የኤሌክትሮኒክ ከዋን:: ሁለቱ መመጪዎች አኖድና ካቶድ ተብለው ይጠራሉ

ክሪክ Jack

ከባድ ነገሮችን ለአጭር ከፍታ ማንሳት የሚያገለግል ቀላል ከዋን

ክራንቻ Sprocket

ከሰንሰለት ጋር በመጣመዱ፣ በሲኒማ ፊልም ጠርዞች ላይ በመስካት ወዘተ... በጠርዙ ዙሪያ ጥርሶች የተቀረፁበት የአቅም ማስተላለፊያ ሽክርክር

ክር Thread

ከቃጫ ወይንም ጥጥ መሰል ነገር በመፍተል ወይንም በማጣመር የተሰራ በጣም ቀጭን ገመድ

ክብ ጥር ቀት Circular pitch

በጥር ቀት ክብ ላይ ከአንዱ ጥርስ እስከ ተከታዩ ጥርስ ድረስ በተመሳሳይ ነጥቦች መካከል ያለው ር ቀት

ክብ መስሪያ Compass

ሁለት ዘንጎች በአንድ በኩል በቀትርት ተያይዘው አንዱ ዘንግ መቁፊያ የሚይዝ አንደኛው ደግሞ ማቆሚያ ሆኖ ክብ ለመስራት የሚያገለግል መሳሪያ /ስእል 49 ይመልከቱ/

ክብ መጋዝ Circular saw

በኩላቡት ላይ ተሰክቶ እየተሽከረከረ የሚቆርጥ ክብ ጥርሳም የመኪና መጋዝ

ክብቃ ፍሬን Disc brake

ክብቃ ከኩላብ ጋር እየተሽከረከረ ሌሎች አካላት በክብቃው ሁለቱም ገፅታዎች ላይ በመጨን ክብቃውን ከነኩላቡ ለማቆም የሚችል የፍሬን አይነት

ክብ አንጓ Circlip

በርሚሉ መሰል የመኪና አካል ከተገጠመ በኋላ በቁመቱ አቅጣጫ እንዳይንሸራተት የሚያግድ ክፍት ቀለበት መሰል አረብረት /ስእል 50 ይመልከቱ/

ክፍት መፍቻ Open-end Wrench

በጉን በኩል በቡሎን ራስ ላይ ተሰክቶ ቡሎኑን ለመፍታት ወይም ለማሰር የሚያገለግል ጫፉ ክፍት የሆነ የእጅ ማቀላጠፊያ /ስእል 51 ይመልከቱ/

ክፍክድ Valve

በማናቸውም ቧንቧዎች ስርአት ውስጥ የፈሳሽርን ፍሰት ለመቆጣጠር የሚያገለ ገል ክፍን

ክፍክድ ምላስ Clack

ስስ የሆነች በቀላሉ በመከፈትና በመክደን የፍሰትን አቅጣጫ የምትቆጣጠር ቆዳ ወይንም ላስቲክ መሰል የክፍክድ አካል

ከረንቲ Current (electric)

በተወሰነ ጊዜ ውስጥ የሚፈሱት የኤሌክትሪክ ሙሌቶች መጠን

ከረንቲ ቅብሽ Electro plating

በከረንቲ ሃይል አማካይነት የአንዱን ንጥረ ነገር አቶሞች ከአንዱ ኤሌክትሮድ ወደ ሌላ ኤሌክትሮድ የማስተላለፊያ ዘዴ:: በዚሁ ዘዴ ሁለተኛው ኤሌክትሮድ የአንደኛውን ኤሌክትሮድ ንጥረ ነገር ቅብ ሊያገኝ ይችላል

ከቲጥርስ Buttress thread

አቀምና ቀለጥፍና እንዲኖረው፣ በልዩ ቅርፅ የተሰራ የቡሎን ጥርስ አይነት

ከፈን Bonnet (hood)

ነገሮች እንዳይሰረቁ ወይንም እንዳይበላሹ የሚያገለግል የመከለከያ ሽፋን

ኳስ ሙላ Ball joint

አንዱ ኳስ መሰል ጫፍ ያለው ነገር ወደ ሌላው አቻው ወደሆነ ክብ መሰኪያ ውስጥ ተገጥሞ በተወሰነ ዘዌ በብዙ አቅጣጫ ሊንቀሳቀስ የሚችል አካል

